# Is Jesus God?

Ahmed Deedat

አሣታሚ



ነጃሺ ማተሚያ ቤት

# ኢየሱስ
# እውን ፈጣሪ ነውን?



# ኢየሱስ እውን ፈጣሪ ነውን?

አዘጋጅ

አህመድ ዲዳት

ትርጉም አሣታሚና አከፋፋይ



ነጃሺ አሣታሚ ድርጅት

1ኛ እትም 1988

ክፍል አንድ

# ኢየሱስ እውን ፈጣሪ ነው?

በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩኅሩኅ በጣም አዛኝ በሆነው።

አንድ ፍጹም አምላክ ብቻ መኖሩን የሚያውጅ ሃይማኖት ቢኖር ኢስላም ብቻ ነው። አንድ ፍፁም አምላክ ሲባል ደግሞ በሁለንተናዊ ባሕሪው ፍፁም አምሳያና ሽሪክ (ተጋሪ) የሌለው ብቸኛ አንድ አምላክ ማለት ነው።

«በል:- እርሱ አላህ አንድ ነው። አላህ (የሁሉ) መጠጊያ ነው። አልወለደም፤ አልተወለደም። ለርሱም አንድም ብጤ የለውም።»

(አል–ኢኽላስ፥ 1–4)

ቤኖኒ (Benoni) በምትባል የደቡብ አፍሪካዊት ከተማ አንድ ሰው ይኖራል። ይህ ሰው በስነ መለኮት ትምህርት የነጠረ ዕውቀት የለውም። ሆኖም ግን ሙስሊሞችን ለማጥመቅ በክርስቶስ የተሾመ የ«ፈጣሪ» መልክተኛ እንደ ሆነ ደጋግሞ በመለፈፍ ራሱን ያታልላል። በጥብቅና ሙያ የሰለጠነው ይህ ሰው፥ ቅንጣት የዐረብኛ ቃል ሳያውቅና ቁርአንን በአግባቡ ሳይረዳ በቃላት በመጫወትና የቅዱስ ቁርአን አንቀጾች ያለ ቦታቸው በመጠቃቀስ በማወናበድ ረገድ በጣም የተካነ ነው። ሙስሊሞችን ኢየሱስ (ዒሳ) (ዐ.ሰ) ፈጣሪ እንደሆነ ለማሳመን ይሻል። ይህ ዓይነቱ እምነት ደግሞ በአላህ ፍጹማዊ አንድነት ላይ እምነታቸውን ለአፀደቁ ሙስሊሞች ከቶውንም የማይዋጥላቸው ብቻ ሳይሆን በአላህ ሉዓላዊና ፍጹማዊ አንድነት ላይ ማሾፍ ሆኖ ይታያቸዋል፤ ስለሆነም ይጠየፉታል።ይህም ብቻ አይደለም።በቅዱስ ቁርአን በግልጽ ሠፍሮ የሚገኘውን የአላህ አዋጅ የሚቃረን ጭምርም በመሆኑም ያወግዙታል። ሆኖም የዚህ መሠሪ ወንጌላዊ ሙስሊሞችን የማታለል ዘዴዎችና ጥረቶች ሁሉ ያለ ጥርጥር ይከሽፋሉ። ምክንያቱም እውነትን በአፈ ጮሌነት መቀልበስ የሚሞከር አይደለምና። ቅዱስ ቁርአን ይህን አስመልክቶ እንዲህ ይለናል:-

«በልም እውነት መጣ፥ውሸትም ይወገድ፤ እነሆ ውሸት ተወጋጅ ነውና፥»

(አል–ኢስራእ፥81)





## ሁለት መላ ምቶች

ኢየሱስ ጌታ (እግዚአብሔር) ለመሆኑ ሰውዬው ሁለት መላ ምቶችን በማስረጃነት ያቀርባል። እነሱም:-

1) «ኢየሱስ ‹አምላክ ነው› ስንል ወይም ‹እግዚአብሔር› እንደሆነ ስንከራከር ‹አብ ነው› ማለታችን አይደለም። የጌታን ባሕሪይ ይጋራል ለማለት ነው።»

2) «ኢየሱስ ከ‹ፈጣሪ› ጋር ሁለንተናዊ የባሕሪይ ተመሳሳይነት እንዳለው እርግጥ ነው። ሆኖም ግን ‹አብ› አይደለም።»

ባጭሩ ሰውዬው ኢየሱስ የእግዚአብሔርን ባሕሪይ የተላበሰና በሁለመናው የ‹ፈጣሪን› ባሕሪይ የሚያንጸባርቅ በመሆኑ በ‹ጌትነቱ› ልንቀበለው እንደሚገባ ነው የሚሞግተን። ሰውየው ቀደም ሲል በጨረፍታ እንደጠቀስነው የጥብቅና ሙያ ባለቤት በመሆኑ አንዳችም አሳማኝነት በሌላቸው፥ፍሬ ቢስ ቃላት ብዙ ቅጾችን የመሙላት ችሎታውን አንጠራጠርም። ይህን እሰጥ አገባ አስነስቶ የኢየሱስን መለኮታዊነት ለማረጋገጥ የሚጠቀምባቸው ስልቶች ስለ ጠበቆችና ስለ ጥብቅና ብዙ ከመናገራቸው ውጭ ቁልጭ ያለውን መጽሐፍ ቅዱሳዊ እውነት የሚያረጋግጡ አይደሉም።

ከዚህ በታች ከመጽሐፍ ቅዱስ አያሌ ጥቅሶችን ዋቢ በማድረግ ኢየሱስ የአምላክን ባሕሪ እንደማይጋራና በምንም መልኩ እግዚአብሔርን እንደማይመስል በማመልከት፥የሰውዬው አባባል መሠረተ–ቢስ መሆኑን ለማሳየት እንሞክራለን።ጥቅሶቹ ላይ የእኛን አስተያየት ሳንጨምር እንዳሉ አስቀምጠናቸዋል። እስኪ ራሱ መጽሐፍ ቅዱስ እንዲናገር እንፍቀድለት። ኢየሱስን– «አምላክ»–«ፈጣሪ»–«እግዚአብሔር»–«ጌታ» እንደሆነ መስበክ በፈጣሪ ታላቅነት ላይ ማሾፍ ብቻ ሳይሆን ወደ ክሕደት የመጨረሻ እርከን የሚያሸቀ ነጥር ነው። የሰው ልጅንም የማመዛዘን ችሎታ የሚያረክስና የሚያኮስስ ስድብ ነው።

ማስታወሻ:-

ከዚህ በታች የሰፈሩት ጥቅሶች ሕጋዊና ይፋዊ ሥርጭት ካለው መጽሐፍ ቅዱስ ነው። በርዕሶቻችንና በንዑስ ርዕሶቻችን ውስጥ አምላክ የሚለውን ቃል

በትምህርተ–ጥቅስ አስቀምጠናል። ይህም ‹ኢየሱስ አምላክ ነው› የሚለውን ጭፍን እምነት የማንቀበል መሆናችንን ለማስመልከት ነው። ኢየሱስ በሚለው ቦታ አምላክ የሚለውን ቃል እየተካን ኢየሱስና አምላክ ተመሳሳይ መሆናቸውን ወይም አለመሆናቸውን እናመሳክር።

## የ«አምላክ» ልደት!

«አምላክ» ከዳዊት ዘር መፈጠሩን ለማመልከት፥ «በሥጋ ከዳዊት ዘር ስለተወለደ» (ወደሮሜ ሰዎች 1፥3)

«ነቢይ ስለሆነ፥ ከወገቡም ፍሬ በዙፋኑ ያስቀምጥ ዘንድ እግዚ አብሔር መሓላ እንደማለለት ስለአወቀ፤» (የሐዋሪያት ሥራ 2፥30)

## የ«አምላክ» የዘር ሐረግ!

«የዳዊት ልጅ የአብርሃም ልጅ የኢየሱስ ክርስቶስ ትውልድ መጽሐፍ» (ማቴዎስ 1፥1)

## የ«አምላክ» ፆታ!

«ሊገርዙት ስምንት ቀን በሞላ ጊዜ በማኅፀን ሳይረገዝ በመልአኩ እንደተባለ፥ ስሙ ኢየሱስ ተብሎ ተጠራ።» (ሉቃስ 2–21)

## ማሪያም «አምላክ»ን ስለ መፀነሷ እና መውለዷ

እንዴት ነው ማሪያም «አምላክ»ን አርግዛ የወለደችው:- ማሪያም እንደ ማንኛዋም ሴት አርግዛ በቀኗ እንደወለደችው ለማመልከት:-

«በዚያም ሳሉ የመውለጃዋ ወራት ደረሰ የበኩር ልጅዋንም ወለደች፥» (ሉቃስ 2፥6)

ይህም ማለት ማሪያም ተፈጥሯዊ የፅንስ ወራቷን እንደማንኛዋም ሴት መፈፀሟን እንረዳለን። የአወላለዷም ሁኔታ በማንኛቸውም መለኪያ ቢሆን ከመሰል ሴቶች የተለየ አልነበረም:-





«እርሷም ፀንሳ ነበር ምጥም ተይዛ ልትወልድ ተጨንቃ ጮኸች» (የዮሐንስ ራዕይ፥12፥2)

## «አምላክ» የሴት ጡት ጠብቷል!

«ይህንም ሲናገር፥ ከሕዝቡ አንዲት ሴት ድምፅዋን ከፍ አድርጋ:- የተሸከመችህ ማኅፀንና የጠባሃቸው ጡቶች ብፁዓን ናቸው አለችው።» (ሉቃስ 11፥27)

## የ«አምላክ» የትውልድ መንደር!

«ኢየሱስም በይሁዳ ቤተልሔም በንጉሡ በሄሮድስ ዘመን በተወለደ ጊዜ፥» (ማቴዎስ 2፥1)

## የ«አምላክ» ሙያ!

«ይህ አናጢው የማሪያም ልጅ የያዕቆብም፥ የዩሳም፥ የይሁዳም፥ የስምዖንም ወንድም አይደለምን?» (ማርቆስ 6፥3)

«የአናጢ ልጅ አይደለምን» (ማቴዎስ 13፥55)

## የ«አምላክ» የመጓጓዣ ዘዴ!

«ለጽዮን ልጅ:- እነሆ፥ንጉሥሽ የዋህ ሆኖ በአህያ ላይና በአህያይቱ ግልገል በውርንጫይቱ ላይ ተቀምጦ ወደ አንቺ ይመጣል በሉአት» (ማቴዎስ 21፥5)

«ኢየሱስ ውርንጫ አግኝቶ በእርሱ ተቀመጠ።» (ዮሐንስ 12፥15)

## የ«አምላክ» ምግብና አስካሪ መጠጥ

«የሰው ልጅ እየበላና እየጠጣመጣ፥እነርሱም:- እነሆ፥በላተኛና የወይን ጠጅ ጠጭ፥የቀራጮችና የኃጢአተኞች ወዳጅ ይሉታል።» (ማቴዎስ 11፥19)

«የሰው ልጅ እየበላና እየጠጣ መጥቶአልና:- እነሆ፥ በላተኛና የወይን ጠጅ ጠጭ፥ የቀራጮችና የኃጢአተኞች ወዳጅ» (ሉቃስ 7፥34)

## የ«አምላክ» ድህነት!

«ኢየሱስም:- ለቀበሮዎች ጉድጓድ ለሰማይም ወፎች መስፈሪያ አላቸው፤ ለሰው ልጅ ግን ራሱን የሚያስጠጋበት የለውም አለው።» (ማቴዎስ 8፥20)

## የ«አምላክ» ቁሳቁሶች!

«... የጫማው ጠፍር....» (ሉቃስ 3፥16)

«ጭፍሮቹም ኢየሱስን በሰቀሉት ጊዜ ልብሶቹን ወስደው ለእያንዳንዱ ጭፍራ አንድ ክፍል ሆኖ በአራት ከፋፈሉት እጀ ጠባቡንም ደግሞ ወሰዱ።» (ዮሐንስ 19፥23)

## አማኝ ይሁዳዊ «አምላክ»!

«ማለዳም ተነስቶ ገና ሌሊት ሳለ ወጣ፥ ወደ ምድረ በዳም ሄዶ በዚያ ፀለየ።» (ማርቆስ 1፥35)

## መልካም ዜጋና ለቄሳርም ታማኝ «አምላክ»!

«የቄሣርን ለቄሣር፥ የእግዚአብሔርንም ለእግዚአብሔር አስረክቡ አላቸው።» (ማቴዎስ 22፥21)

## ግብር ከፋይ «አምላክ»!

«ወደ ቅፍርናሆምም በመጡ ጊዜ ግብር የሚቀበሉ ሰዎች ወደ ጴጥሮስ ቀረቡና:- መምህራችሁ ሁለቱን ዲናር አይገብርምን? አሉት። አዎን ይገብራል አለ።» (ማቴዎስ17፥24–25)





## የ«አምላክ» ቤተሰብ!

«አምላክ» የዮሴፍ ልጅ ነበር:- «ፊልጶስ ናትናኤልን አግኝቶ:- ሙሴ በሕግ–ነቢያትም ስለ እርሱ የጻፉትን የዮሴፍን ልጅ የናዝሬቱን ኢየሱስን አግኝተነዋል አለው።» (ዮሐንስ 1፥46)

## የ«አምላክ» ወንድሞች!

«ወደ ገዛ አገሩም መጥቶ እስኪገረሙ ድረስ በምኩራባቸው ያስተምራቸው ነበር፤ እንዲህም አሉ:-ይህን ጥበብና ተዓምራት ይህ ከወዴት አገኘው? ይህ የጸ ራቢ ልጅ አይደለምን? እናቱስ ማሪያም ትባል የለምን? ወንድሞቹስ ያዕቆብና ዮሳ፥ ስምዖንም፥ ይሁዳም አይደሉምን? እኅቶቹስ ሁሉ በእኛ ዘንድ ያሉ አይደሉምን?» (ማቴዎስ 13፥ 54–56)

የ«አምላክ» መንፈሳዊ እድገት:- «ሕፃኑም ጥበብም ሞልቶበት በመንፈስ ጠነከረ፥» (ሉቃስ 2፥40)

የ«አምላክ» አዕምሮአዊ አካላዊ ባሕርያዊ እድገት:-«ኢየሱስም ደግሞ በጥበብና በቁመት በሞገስም በእግዚአብሔርና በሰው ፊት ያድግ ነበር።» (ሉቃስ 2፥52)

ወላጆቹ ወደ ኢየሩሳሌም ሲወስዱት «አምላክ» 12 ዓመት ሞልቶት ነበር። «ወላጆቹም በየዓመቱ በፋሲካ በዓል ወደ ኢየሩሳሌም ይወጡ ነበር። የአሥራ ሁለት ዓመት ልጅ በሆነ ጊዜ እንደ በዓሉ ሥርዓት ወደ ኢየሩሳሌም ወጡ፤» (ሉቃስ 2፥41–42)

## አቅመ ቢሱ «አምላክ»!

«እኔ ከራሴ አንዳች ላደርግ አይቻለኝም፤ እንደሰማሁ እፈርዳለሁ ፍርዴም ቅን ነው፥ የላከኝን ፈቃድ እንጂ ፈቃዴን አልሻምና።» (ዮሐንስ 5፥30)

## «አምላክ» ስለ ምፅዓት አያውቅም!!

«ስለዚያች ቀን ወይም ስለዚያች ሰዓት ግን የሰማይ መላእክትም ቢሆኑ ልጅም ቢሆን ከአባት በቀር የሚያውቅ የለም።» (ማርቆስ 13፥32)

## «አምላክ» ወቅት መለየት አቃተው!!

«ኢየሱስም ወደ ኢየሩሳሌም ወደ መቅደስ ገባ፤ ዞሮ ብሎም ሁሉን ከተመለከተ በኋላ፥ ጊዜው መሽቶ ስለነበረ ከአሥራ ሁለቱ ጋር ወደ ቢታንያ ወጣ። በማግስቱም ከቢታንያ ሲወጡ ተራበ። ቅጠልም ያላት በለስ ከሩቅ አይቶ ምናልባት አንዳች ይገኝባት እንደሆነ ብሎ መጣ። ነገር ግን የበለስ ወራት አልነበረምና መጥቶ ከቅጠል በቀር ምንም አላገኘባትም።» (ማርቆስ 11፥12–13)

## «አምላክ» አልተማረም!!

«አሁንም በበዓሉ እኩሌታ ኢየሱስ ወደ መቅደስ ወጥቶ ያስተምር ነበር። አይሁድም:- ይህ ሰው ሳይማር መጻሕፍትን እንዴት ያውቃል? ብለው ይደነቁ ነበር።» (ዮሐንስ 7፥14–15)

## «አምላክ» ከልምድ ዕውቀት ገብይቷል!!

«እግዚአብሔርንም ስለ መፍራቱ ተሰማለት፤ ምንም ልጅ ቢሆን፥ ከተቀበለው መከራ መታዘዝን ተማረ፤» (ወደ ዕብራዊያን፥ 5–8)

## «አምላክ» በሰይጣን ተፈተነ!

«አምላክ» ለአርባ ቀናት በሰይጣን ተፈተነ:- «ወዲያውም መንፈስ ወደ ምድረ በዳ አወጣው፤ በምድረ በዳም በሰይጣን እየተፈተነ አርባ ቀን ሰነበተ። ከአራዊትም ጋር ነበረ።» (ማርቆስ፥ 12–13)

«አምላክ» ሳያሰልስ በሰይጣን ተፈተነ:- «ዲያቢሎስም ፈተናውን ሁሉ ከጨረሰ በኋላ እስከ ጊዜው ከእርሱ ተለየ። (ሉቃስ 4፥13)





«አምላክ» እንደ ኃጢአን ሁሉ በሁሉም ይፈተናል:- «ከኃጢአን በቀር በነገር ሁሉ እንደ እኛ የተፈተነ ነው እንጂ» (ወደ ዕብራዊያን 4፥15)

እውነተኛ «አምላክ» በእኩይ ነገሮች አይፈተንም:-«ማንም ሲፈተን በእግዚአብሔር እፈተናለሁ አይበል፤እግዚአብሔር በክፉ አይፈተንምና፤እርሱ ማንንም አይፈትንም።ነገር ግን እያንዳንዱ በራሱ ምኞት ሲሳብና ሲታለል ይፈተናል።» (የያዕቆብ መልዕክት 1፥13–14)

## የ«አምላክ» ተልዕኮ

«አምላክ» ኃጢአቱን ተናዘዘ ንስሐም ገባ:- «ያን ጊዜ ኢየሱስ በዮሐንስ ሊጠመቅ ከገሊላ ወደ ዮርዳኖስ መጣ።» (ማቴዎስ 3፥13)

«ኃጢአታቸውንም እየተናዘዙ በዮርዳኖስ ወንዝ ከእርሱ ይጠመቁ ነበር።» (ማቴዎስ 3፥6)

## «አምላክ» ኃጢአንን ሊያንፃ አልመጣም!!

«ብቻውንም በሆነ ጊዜ፥ በዙሪያው የነበሩት ከአሥራ ሁለቱ ጋር ስለምሳሌው ጠየቁት። እንዲህም አላቸው:- ከእናንተ የእግዚአብሔርን መንግሥት ምሥጢር ማወቅ ተሰጥቶአችኋል፤ በውጭ ላሉት ግን፥ አይተው እንዲያዩ እንዳይመለከቱም፥ሰምተውም እንዲሰሙ እንዳያስተውሉም እንዳይመለሱ ኃጢአታቸውም እንዳይሰረይላቸው» (ማርቆስ 4፥10–12)

## ዘረኛ «አምላክ»

ነገደ ይሁዳ «አምላክ»:- «እነሆ፥ ከይሁዳ ነገድ የሆነው አንበሳ» (የዮሐንስ ራእይ 5፥5)

ለይሁዶች ብቻ የመጣው «አምላክ»:- «እርሱም መልሶ:- ከእስራኤል ቤት ለጠፉት በጎች በቀር አልተላክሁም አለ።» (ማቴዎስ 15፥24)

የ«አምላክ» የዘር መድሎ:- «እነዚህን አስራ ሁለቱን ኢየሱስ ላካቸው፥ አዘዛቸውም፥ እንዲህም አለ:- በአሕዛብ መንገድ አትሂዱ፥ ወደ ሳምራውያንም ከተማ አትግቡ፤ ይልቅስ የእስራኤል ቤት ወደሚ ሆኑ ወደ ጠፉት በጎች ሂዱ እንጂ።» (ማቴዎስ 10፥5:6)

አሕዛብ (አይሁድ ያልሆኑ) በ«አምላክ» አመለካከት ውሾች ናቸው:- «እርሱ ግን መልሶ:- የልጆችን እንጀራ ይዞ ለቡችሎች መጣል አይገባም አለ።» (ማቴዎስ 15፥26)

## የ«አምላክ» መንግስት!

«በያዕቆብ ቤትም ላይ ለዘላለም ይነግሣል፤ ለመንግሥቱም መጨረሻ የለውም።» (ሉቃስ 1፥33)

## የ«አምላክ» የማዕረግ ስሞች:-

«የአይሁድ ንጉሥ» (ማቴዎስ 2–2)

«የእስራኤል ንጉሥ» (ዮሐንስ 1፥49)

«ኢየሱስ ወደ ኢየሩሳሌም እንዲመጣ በሰሙ ጊዜ፥ የዘንባባ ዛፍ ዝንጣፊ ይዘው ሊቀበሉት ወጡና:- ሆሳዕና በጌታ ስም የሚመጣ የእስራኤል ንጉሥ» (ዮሐንስ 12፥13)

## የማይመስል «አምላክ»

«አምላክ» ተራበ!

«አርባ ቀንና አርባ ሌሊትም ከጦመ በኋላ ተራበ።» (ማቴዎስ 4፥12)

«በማለዳም ወደ ከተማ ሲመለስ ተራበ።» (ማቴዎስ 21፥18)

«በማግስቱም ከቢታንያ ሲወጡ ተራበ።» (ማርቆስ 1፥12)





## «አምላክ» ተጠማ!

«ተጠማሁ አለ» (ዮሐንስ 19፥28)

## «አምላክ» አንቀላፋ!

«እርሱ ግን ተኝቶ ነበር።» (ማቴዎስ 8፥24)

«ሲሄዱም አንቀላፋ።» (ሉቃስ 8፥23)

«እርሱም በስተኋላዋ ትራስ ተንተርሶ ተኝቶ ነበር።» (ማርቆስ 4፥38)

## «አምላክ» ታከተው!

«ኢየሱስም መንገድ ከመሔድ ደክሞ በጉድጓድ አጠገብ እንዲህ ተቀመጠ፤» (ሐንስ 4፥6)

## «አምላክ» ታወከ !

«በመንፈሱ አዘነ፥ በራሱም ታወከ፤» (ዮሐንስ 11፥33)

## «አምላክ» አነባ!

«ኢየሱስም እንባውን አፈሰሰ።» (ዮሐንስ 11፥35)

## «አምላክ» ተከዘ!

«ሊያዝንም ሊተክዝም ጀመረ።» (ማቴዎስ 26፥38)

«ነፍሴ እስከ ሞት ድረስ እጅግ አዘነች፣» (ማቴዎስ 26፥38)

የ«አምላክ» ድንጋጤ:- «ሊደነግጥም ሊተክዝም ጀመረና ነፍሴ እስከ ሞት ድረስ እጅግ አዘነች፤» (ማርቆስ 14፥34)

## ደካማ «አምላክ»!

«ከሰማይም መጥቶ የሚያበረታው መልአክ ታየው።» (ሉቃስ 22፥43)

## ጦረኛ «አምላክ»!

ጉልበተኛው «አምላክ»:- «የአይሁድ ፋሲካም ቀርቦ ነበር፥ ኢየሱ ስም ወደ ኢየሩሳሌም ወጣ። በመቅደስም በሬዎችንና በጐችን ርግቦችንም የሚሸጡትን ገንዘብ ለዋጮችንም ተቀምጠው አገኘ፤ የገመድ ጅራፍ አበጅቶ ሁሉን በጐችንም በሬዎችንም ከመቅደስ አወጣ ቸው፥ የለዋጮችንም ገንዘብ አፈሰሰ ገበታዎቻቸውንም ገለበጠ፥» (ዮሐንስ 2፥13:15)

የ«አምላክ» የክተት አዋጅ:- «በምድር ላይ ሰላምን ለማምጣት አይምሰላችሁ፤ ሠይፍን እንጂ ሰላምን ለማምጣት አልመጣሁም።» (ማቴዎስ 10፥34)

«የሌለውም ልብሱን ሸጦ ሰይፍ ይግዛ።» (ሉቃስ 22፥36)

## «አምላክ» በስጋት ተንከራተተ !

«አምላክ» በፍርሃት ተዋጠ:- «ከዚህም በኋላ ኢየሱስ አይሁድ ሊገድሉት ይፈልጉ ስለነበር በይሁዳ ሊመላለስ አይወድም ነበርና በገሊላ ይመላለስ ነበር።» (ዮሐንስ 7፥1)

«እንግዲህ ከዚያ ቀን ጀምረው ሊገድሉት ተማከሩ። ከዚያ ወዲያም ኢየሱስ በአይሁድ መካከል ተገልጦ አልተመላለሰም፤» (ዮሐንስ 11፥153–54)

## «አምላክ» ከእጃቸው አፈተለከ!

«እንግዲህ ደግመው ሊይዙት ፈለጉ፤ ከእጃቸውም ወጣ።» (ዮሐንስ 10፥39)





«ስለዚህ ሊወግሩት ድንጋይ አነሱ፤ ኢየሱስ ግን ተሰወራቸው ከመቅደስም ወጠቶ በመካከላቸው አለፍ ሔደ።» (ዮሐንስ 8፥ 59)

## የ«አምላክ» መማረክ

በጓደኛ ክሕደት «አምላክ» የተደበቀበት ቦታ ታወቀ። «ኢየሱስም ደቀ መዛሙርቱም ብዙ ጊዜ ወደዚያ ስለተሰበሰቡ አሳልፎ የሰጠው ይሁዳ ደግሞ ስፍራውን ያውቅ ነበር። ስለዚህ ይሁዳ ጭፍሮችንና ከካሕናት አለቆች ከፈሪሳውያንም ሎሌዎችን ተቀብሎ በችቦና በፋና በጋሻ ጦርም ወደዚያ መጣ።» (ዮሐንስ 18፥2–3)

«አምላክ» ተማረከ፥ ታስሮም ተወሰደ:- «እንግዲህ የሻለቃውና ጭፍሮቹ የአይሁድም ሎሌዎች ኢየሱስን ይዘው አሰሩት፥» (ዮሐንስ፥ 18፥12–13)

## «አምላክ» ተዋረደ!!

«ኢየሱስንም የያዙት ሰዎች ይዘብቱበትና ይደበድቡት ነበር፤ ሸፍነውም ፊቱን ይመቱት ነበርና፤» (ሉቃስ 22፥63–64)

«በዚያን ጊዜ በፊቱ ተፉበት ጐሰሙትም፥ ሌሎችም በጥፊ መትተው:-» (ማቴዎስ 26፥67)

## «አምላክ» አማረረ፥ መድረሻ አጣ!!

«ይህንም ሲል በዚያ ቆሞ የነበረው ከሎሌዎች አንዱ:-ለሊቀ ካህናቱ እንዲህ ትመልሳለህን? ብሎ ኢየሱስን በጥፊ መታው። ኢየሱ ስም መልሶ ክፉ ተናግሬ እንደሆንሁ ስለ ክፉ መስክር፤ መልካም ተናግሬ እንደሆንሁ ግን ስለ ምን ትመታኛለህ?» (ዮሐንስ18፥22–23)

## «አምላክ» ሞት ተፈረደበት!.!

«እነርሱም ሁሉ:- ሞት ይገባዋል ብለው ፈረዱበት።» (ማርቆስ 14፥64)

«እነርሱም:- ሞት ይገባዋል ብለው መለሱ።» (ማቴዎስ 26፥66)

## የ«አምላክ» የጣር ጩኸት!

«ኢየሱስ:- ኤሎሄ ኤሎሄ ላማ ሰበቅታኒ? ብሎ በታላቅ ድምፅ ጮኸ። ይህም:- አምላኬ፥ አምላኬ፥ ስለምን ተውኸኝ? ማለት ነው።» (ማቴዎስ 27፥46)

## «አምላክ» እንደ ገራም እንስሳ!

«እንደ በግ ወደ መታረድ ተነዳ፥ የበግ ጠቦትም በሸላቹ ፊት ዝም እንደሚል፥ እንዲሁ አፉን አልከፈተም።»(የሐዋሪያት ሥራ፥ 8፥32)

## «አምላክ» ሞተ ተብሎ ተገመተ!

ሟች «አምላክ»:- «ኢየሱስም በታላቅ ድምፅ ጮኸ ነፍሱንም ሰጠ።» (ማርቆስ 15፥37) «ስለ ኃጢአተኞች ሞቶአልና።» (ወደሮሜሰዎች 5፥5) «...ፈጽሞ እንደሞተ አይተው....» (ዮሐንስ 19፥33)

## የ«አምላክ» አስከሬን

«ይኸውም ወደ ጲላጦስ ቀርቦ የኢየሱስን ሥጋ ለመነው። ጲላጦስም እንዲሰጡት አዘዘ። ዮሴፍም ሥጋውን ይዞ በንጹሕ በፍታ ከፈነው፥» (ማቴዎስ 27፥58–59)

## ሊታዘንለት የሚገባ «አምላክ»!

«የመቶ አለቃውም የሆነውን ነገር ባየ ጊዜ ይህ ሰው በእውነት ፃድቅ ነበር ብሎ እግዚአብሔርን አከበረ።»

## ማጠቃለያ

ራሱን (የኢየሱስ) መልዕክተኛ አድርጐ የሚቆጥረው የደቡብ አፍሪካው ወንጌላዊ «ኢየሱስ አምላክ ነው» ይለናል። እንዴት? ሲባል የሚሰጠው ምክንያት





1) የአምላክን ባሕሪያት በመጋራቱ

2) በሁሉም መልኩ አምላክን (እግዚአብሔርን) ስለሚመስል የሚል መልስ ይሰጣል።

ነገር ግን እስከ አሁን ከመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ስለ ኢየሱስ ከላይ የተጠቀሱት አንቀጾች ሁሉ ኢየሱስ፥ የአምላክን (የእግዚአብሔርን) ባሕሪያት የማይጋራና በምንም ዓይነት አምላክን እንደማይመስል በማያሻማ መልኩ የሚያረጋግጡ ሆነው እናገኛቸዋለን። ፈጣሪም እንዳልሆነ በቁርጠኝነት መስክረዋል። ስለሆነም ለደቡብ አፍሪካው «ወንጌላዊ» ሁለት አማራጮች ቀርበውለታል። አንድም «ዒሳ» (ዐ.ሰ) (ኢየሱስ) ፈጣሪ ነው የሚለውን እምነቱን በማስረጃ የማጽደቅ፥ አሊያም ከአንድ በላይ አምላክ የሚያመልክ ሙሽሪክ (አጋሪ) መሆኑን በይፋ ማሳወቅ አለበት። ጤፍ የሚቆላ ምላሱን እያንጣጣ ከላይ ወደታች ከታች ወደ ላይ ቢዘል «ዒሳ አላህ ነው» ብሎ ሙስሊሞችን ማሳመን ከቶውንም ቢሆን የሚቻል አይደለም። እሱና ባልደረቦቹ መሠረት በሌለው ከንቱ ልፋት፥ ዒሳን ከሰብዓዊ ፍጡርንትና ከነቢይነት ወደ አምላክነት ደረጃ እንዲያሸጋግሩት ሙስሊሞችን ለማወናበድ የሚያደርጉት መፍጨርጨር ከቶውንም አይሳካም። ዒሳ (ዐ.ሰ) ወደ እስራኤል ሰዎች አንድ መሠረታዊ ብሥ ራት አንግቦ የመጣ መሆኑን ሙስሊሞች በጽኑ ያምናሉ። ያም በምድር ላይ የአላህ መንግስት እንደሚመጣ የሚያመለክት ትምቢት ሲሆን፥ በነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) መነሳት እውን ሆኗል። ይህ ነው የማያወላውለው የሙስሊሞች እምነት።

ክፍል ሁለት

# የዮናስ ምልክት

# «ክርስቶስ» ስም አይደለም

በአሁኑ ወቅት በዓለም ላይ የሚገኙ ከአንድ ሺህ ሚሊዮን በላይ የሚሆኑት የክርስትና እምነት ተከታዮች የናዝሬቱ ኢየሱስ «ክርስቶስ» እንደሆነ በጭፍን ይቀበላሉ። ለዚህም አቋማቸው ማጠናከሪያ ይሆኑ ዘንድ «አንድ ሺህ አንድ» ትንቢቶችን ከአይሁዶች መጽሐፍ ቅዱስ (ከብሉይ ኪዳን መጽሐፍ) እየለቃቀሙና እያገጣጠሙ፥ ኢየሱስ አዳኛቸው «መሲሐቸው» መሆኑን በመረጃ ለማስደገፍ ይፍጨረጨራሉ። «አንድ ሺዎቹን» ትንቢቶች ለጊዜው ወደ ጐን አድርገን ኢየሱስ ራሱ በሐዲስ ኪዳን ውስጥ በማያሻማ ሁኔታ የእርሱን ማንነት ሊያረጋግጥ የሚችል ምልክት እንደሚያሳይ ለአይሁድ ቃል ገብቶላቸው ነበር። የገባላቸውን ቃል ኪዳን ፈጽሞላቸው እንደሆነ ለአንድ አፍታ እንመርምር።

መጀመሪያ «ክርስቶስ» የሚለው ቃል ተውላጠ ስም አለመሆኑን መረዳት አለብን። ማዕረግን ጠቋሚ ቅጽል ነው። «ክርስቶስ» የሚለው የግሪክ ቃል «መሲያህ» የሚለው የእብራይስጥ ቃል ቀጥተኛ ትርጉም ነው። በእንግሊዝኛ «anointed» የሚለው ቃል የሚተካው ሲሆን፥ ወደ አማርኛ ሲመለስ ደግሞ «የተቀባ» የሚል ትርጓሜ ይኖረዋል። «የተቀባ» ለሚለው ቃል በግሪክ ቋንቋ የምናገኝለት ፍች ክርስቶስ የሚል እንደሆነ ጠቅሰናል። እንግሊዝኛ ተናጋሪዎች «Christos»– ክርስቶስ– ከሚለው የግሪክ ቃል ውስጥ «O» እና «S» በማውጣት «Christ» ክራይስት–የሚል አዲስ ቃና ያለው ቃል እንደፈጠሩ መገንዘብ አያዳግትም።

በጥንት ዘመን ቀሳውስት ለቤተ–ክህነት ሹመት ሲበቁ፥ነገሥታትም በትረ–ሥልጣን ሲጨብጡ የቅብዓት ሥርዓት ይፈጽማሉ። በዚህን ጊዜ «የተቀቡ» (anointed) ይባላሉ። መጽሐፍ ቅዱስ የአሕዛብ ንጉሥ ስለነበረው ስለ ቂሮስ ሥልጣን መያዝ ሲተርክ «anointed» የሚለውን ቃል ተጠቅሞበታል። (ትንቢተ–ኢሳያስ 45፥1)





## የሉቃስ ወንጌል እንዲህ ሲል ያስታውሰናል:-

«ሊገርዙት ስምንት ቀን በሞላ ጊዜ፥ በማኅፀን ሳይረገዝ በመልአኩ እንደ ተባለ፥ ስሙ ኢየሱስ ተብሎ ተጠራ።» (ሉቃስ 2፥21)። ከዚህ የምንገነዘበው በመልአኩ አማካኝነት ገና ያልተወለደ ልጁን ትጠራበት ዘንድ የተነገራት ስም ኢየሱስ እንጂ ክርስቶስ (የተቀባ) አልነበረም። በመጥምቁ ዮሐንስ እጅ ከተጠመቀ በኋላ ነው ክርስቶስ (የተቀባ) የሚለው ቅጽል የታከለለት። ይህንን የማዕረግ ቅጽል አይሁድ እንዳለ ለመቀበል ፈቃደኛ አልሆኑም። «የተቀባ» ለመሆኑ መረጃ እንዲያቀርብ ጠየቁ።

## ተዓምር እንደ ማስረጃ

ማቴዎስ እንደሚተርክልን ከአይሁድ ምሁራኖች–ከጻፎችና ከፈሪሳውያን–መካከል ወደ ኢየሱስ በመምጣት እንዲህ ሲሉ ጠየቁት:- «መምህር ሆይ! ከአንተ ምልክት እንድናይ እንወዳለን አሉ።» (ማቶዎስ 12፥38)። በእርግጥ እነሱ የፈለጉት አንዳች «ምትሃታዊ ትዕይንት» እንዲያሳያቸው ነበር። አስማተኞች የሚሰሩዋቸውን ከባርኔጣ ስር ጥንቸል ማውጣት ወይም በባሕር ላይ መራመድ አለያም በሕዋ ላይ መንሳፈፍ ያም ካልሆነ በፍም እሳት ላይ በባዶ እግር መሄድ አይነት ትዕይንት ለማየት ጓጉተዋል። አይሁድ ኢየሱስን እንደ ተራ ምትሃተኛ ነበር የቆጠሩት።

## አንድ ብቻ «ምልክት»

የአይሁድ ምሁራን ተአምር እንዲያሳያቸው ችክ በማለታቸው ኢየሱስ በቁጣ ስሜት እየተብከነከነ እንዲህ አላቸው:- «ክፉና አመንዝራ ትውልድ ምልክት ይሻል፥ ከነቢዩ ከዮናስ ምልክት (ተአምር) በቀር ምልክት አይሰጠውም። ዮናስ በዓሣ ነባሪ ሆድ ሦስት ቀንና ሦስት ሌሊት እንደ ነበረ፥ እንዲሁም የሰው ልጅ በምድር ልብ ሦስት ቀንና ሦስት ሌሊት ይኖራል።» (ማቴዎስ 12፥39–40)። ኢየሱስ ለአይሁድ በግልጽ የነገራቸው «አንዳችም ምልክትን (ተአምር») የእሱን መሲህነት (ክርስቶስነት) እንደማያረጋግጥ ነው። የእርሱን መሲህነት የሚያረጋግጥ ነገር አንድ ብቻ ነው። የእርሱ ፍጻሜ ከዮናስ ፍጻሜ ጋር ተመሳሳይ እንደሚሆን ትንቢት ተናግሯል። ይህ ትንቢት (ማቴዎስ 12፥39–40) መፈጸሙን ሲያረጋግጡ ክርስቶስ መሆኑን ይረዱታል። ኢየሱስ

ለክርስቶስነቱ ለአይሁድ በርጤሜዎስ የተባለ ሰው ዓይን ማብራቱን በማስረጃነት አልጠቀሰም። የልብሱን ጫፍ በጣቶቿ በመንካቷ ብቻ ከበሽታዋ የተፈወሰችውን ሴትም አላወሳም። ሁለት ሺህ ያህል አሳማዎችን በማጥፋት በእርኩስ መንፈስ ከተለከፈ ሰው አጋንንት ማውጣቱን በዋቢነት አልጠቀመም። አምስት ሺህ እና ሦስት ሺህ የሚሆኑ ሰዎችን በቁራሽ ዳቦና ዓሣ መግቦ ማጥገቡንም በእማኝነት አላቀረበም። ኢየሱስ ምልክት (ተአምር) የሚለው ነገር አንድ ብቻ ነው። ያም የነቢዩ ዮናስ ምልክት ነው። እንደ እንግሊዞች ብሂል «እንቁላሎቹን ሁሉ በአንድ ቅርጫት ውስጥ አስቀመጠ።» የእርሱ ክርስቶስ መሆን ወይም አለመሆን የሚረጋገጠው ወደፊት ሊያሳያቸው ቃል በገባላቸው ምልክት ብቻ ነው።

ኢየሱስ አሳያለሁ ያለውን ብቸኛ ምልክት አሳይቷልን?ለሚለው ጥያቄ ክርስቲያኖች ሁሉ ሳያቅማሙ የሚሰጡት መልስ «እንዴታ!» የሚል ነው። «ነገሮችን በጥንቃቄ ሳትመረምሩ መደምደሚያ ላይ ለመድረስ አትጣደፉ» የሚል መንፈስ ያለውን የመጽሐፍ ቅዱስ ምክር ደንታም ያላቸው አይመስልም።

«ሁሉን ፈትኑ መልካሙንም ያዙ፤» (1ኛ ተሰሎንቄ 5፥21)

## ዮናስ ከአምላክ መልዕክት ሸሸ

የ«ዮናስ ምልክት (ተአምር)» ምንድን ነበር? ይህን ጉዳይ ለመረዳት ብሉይ ኪዳንን መለስ ብለን እናገላብጥ። ዮናስ ወደ ነነዌ በመሄድ እያንዳንዱ ነዋሪ ንስሐ እንዲገባ፥ ከእኩይ መንገድ እንዲመለስ፥ ግፍና ጭካኔ ያበቃ ዘንድ እንዲያስተምር ላከው። (ዮናስ 1፥2 ፣ 3፥8)። ሆኖም ግን ዮናስ ወደ ነነዌ መሄድን እጅግ አድርጐ ተጠየፈ። ወደ ነነዌ ከመሄድ ይልቅ የእግዚአብሔርን ትዕዛዝ በመጣስ ወደ ተርሴስ መኰብለልን መረጠ። በመርከብ ተሳፍሮ ጉዞ ጀመረ። በባሕር ላይ እያለ በኃይለኛ ማዕበል መርከቧ ተመታች። የመርከቧ ተሳፋሪዎች በድንጋጤ ተዋጡ። በወቅቱ መርከበኞች አንድ አጉል እምነት ነበራቸው። ይኸውም «በባሕር ላይ እንዲህ ዓይነት ቀውጢ የሚፈጠረው ከጌታው ትዕዛዝ የኰበለለ ሰው በመርከቧ ውስጥ ሲገኝ ነው» የሚል ነበር። እርስ በርሳቸው ከተወያዩ በኋላ ይህን ሰው ለይቶ ለማውጣት ዕጣ መጣጣል እንደሚያስፈልግ ወሰኑ። ከመጽሐፍ ቅዱስ ለመጥቀስ:- «ይህ ክፉ ነገር በማን ምክንያት እንዳገኘን እናውቅ ዘንድ ኑ፥ ዕጣ እንጣጣል ተባባሉ። ዕጣም





ተጣጣሉ፥ ዕጣውም በዮናስ ላይ ወደቀ።» (ዮናስ 1፥7)። ምንም እንኳ ዮናስ ለጊዜው የጌታውን ተልዕኮ ከመፈጸም ወደ ኋላ ቢያፈገፍግም መርከበኞቹንና ተሳፋሪዎቹን ለመታደግ ሲል ራሱን ለመስዋዕትነት የማዘጋጀት ወኔና በጐ ፈቃድ ነበረው። ባሕሩን ሞገዱ ማናወጡን ቀጥሏል። በማዕበል ተመተው እንዳይሰጥሙ ዘዴ መቀየስ ነበረባቸው። ዮናስን ባሕር ውስጥ ላለመጣል የተቻላቸውን ሁሉ አደረጉ። ሆኖም ግን አልተሳካም። በመጨረሻ ምን ማድረግ እንዳለባቸው ጠየቁት። «እርሱም:- ይህ ታላቅ ማዕበል በእኔ ምክንያት እንዳገኛችሁ አውቃለሁና አንስታችሁ ወደ ባሕር ጣሉኝ፥ ባሕሩም ጸጥ ይልላችኋል አላቸው።» (ዮናስ 1፥12)

## ሙት ወይስ ሕያው

ዮናስ ራሱን ለመስዋዕትነት ያቀረበ በመሆኑ ወደ ባሕር ውስጥ ከመጣላቸው በፊት ደብድበው እንዲደክም ማድረግ አላስፈለጋቸውም። እጆቹና እግሮቹን መስበር ወይም በጦር መሣሪያ ማቁሰልም ጥቅም የለውም። ራሱ «አንስታችሁ ወደ ባሕር ጣሉኝ» ብሎ ፈቃደኝነቱን ገልጾላቸዋልና። እዚህ ላይ ጥያቄ ይነሳል። የመርከቡ ካፒቴንና መርከበኞቹ ከመርከቧ አውጥተው ወደ ባሕር ወረወሩት፤ በዚህ ወቅት ዮናስ ሞቷል ወይስ ሕያው ነበር? ማንኛውም የሰንበት ትምህርት የተካፈለ ሕፃን ክርስቲያን እንኳ ሳይቀር የሚሰጠው ቅጽበታዊ መልስ «ሕያው» የሚል ይሆናል። ሞገዱ ባሕሩን ማናወጡን አቆመ። ምናልባት አጋጣሚ ሊሆን ይችል ይሆን? ዓሣ ነባሪ ዮናስን ዋጠው። ዮናስ በግዙፍ ዓሣ በተዋጠበት ቅጽበት ሙት ወይስ ሕያው ነበር? አሁንም መልሱ «ሕያው ነበር» የሚል ይሆናል። «ዮናስም በዓሳው ሆድ ውስጥ ሆኖ ወደ አምላኩ ወደ እግዚአብሔር ጸለየ፥» (ዮናስ 2፥2)። ይህን ጸሎት በሚያደርስበት ወቅት ዮናስ ሕያው እንደነበር ግልጽ ነው። ምክንያቱም ሙት አይጮኽም፥ አይጸልይምም። ለሦስት ቀንና ለሦስት ሌሊት ዓሳው በባሕሩ ውስጥ አንሸራሸረው። ይህ ሲሆን ዮናስ ሞቷል ወይስ ሕያው ነበር? መልሱ አሁንም «ሕያው ነበር» ይሆናል። በሦስተኛው ቀን ዓሣው በየብስ ላይ ሲተፋው ሙት ወይስ ሕያው ነበር? በእርግጥ ሕያው ነበር። ኢየሱስ ስለ ራሱ የተናገረው ትንቢት ምንድን ነው? «...ዮናስ በዓሣ ነባሪ ሆድ ሦስት ቀንና ሦስት ሌሊት እንደ ነበረ፥ እንዲሁ (እንደ ዮናስ) የሰው ልጅ በምድር ልብ ሦስት ቀንና ሦስት ሌሊት ይኖራል።» የዮናስ ሁኔታ እንዴት ነበር? ለሦስት ቀንና ለሦስት ሌሊቶች ሙት ወይስ ሕያው ነበር? ማንኛውም አይሁድ፥ ክርስቲያን እንዲሁም ሙስሊም በአንድነት «ሕያው ነበር» በማለት ይስማማሉ።

## እንደ ዮናስ ሳይሆን

ዮናስ በዓሣ ሆድ ውስጥ ለሦስት ቀንና ለሦስት ሌሊት ሕያው እንደሆነ ሁሉ ኢየሱስም በመቃብሩ ውስጥ ሕያው መሆኑን አስቀድሞ ተንብዮልናል። ነገር ግን ክርስቲያኖች «እነሱን ለማዳን ሲል እንደሞተላቸው» እየተረኩ በዚሁ እምነታቸው ላይ ችክ ይላሉ። ለሦስት ቀንና ለሦስት ሌሊት እንደ ዮናስ ሕያው ሳይሆን ቀርቶ ይሆን? በትንቢቱና በፍጻሜው መካከል ያለው ተቃርኖ ግልጽ ነው። ዮናስ ሕያው ሲሆን ኢየሱስ ሞቷል!! ከዮናስ ጋር በፍጹም አይመሳሰልም። ኢየሱስ የተነበየው «እንደ ዮናስ (Like Jonah)» በማለት እንጂ «እንደ ዮናስ ሳይሆን (Unlike Jonah)» ብሎ አልነበረም። «ኢየሱስ ሞቷል» የሚለው መላ ምት እውነት ከሆነ ኢየሱስ በራሱ ቃል መሠረት የአይሁድ ሐቀኛ መሲህ (ክርስቶስ) አለመሆኑን አረጋግጧል። ምክንያቱም በብቸኝነት እንዲጠባበቁት ያስገነዘባቸው የዮናስ ተአምር እውን ሊሆን አልበቃም። የወንጌል ጸሐፊዎች ትረካ እውነት እንደሆነ የምንቀበል ከሆነ አይሁድ ኢየሱስን «ክርስቶስ ነው ብለው» ባለመቀበላቸው ልንኮንናቸው አይገባም።

## 72 ሰዓታት

የሥነ–መለኮት ጠበብትና የሃይማኖቱ ሊቃውንት በማቴዎስ ወንጌል 12፥40 ኢየሱስ በአጽንኦት ለማመልከት የሞከረው የጊዜውን ተመሳሳይነት «ዮናስ በዓሣ ነባሪ ሆድ ሦስት ቀንና ሦስት ሌሊት እንደነበረ፥ እንዲሁ የሰው ልጅ በምድር ልብ ሦስት ቀንና ሦስት ሌሊት ይኖራል።»–ተመሳሳይነት እንደሆነ ያስገነዝባሉ። «በጥንቃቄ እናስተውል» ይላሉ። እነዚሁ የሥነ–መለኮት ሊቃውንት «በዚህ አንቀጽ ውስጥ ‹ሦስት› የሚለው ቃል ለአራት ጊዜ ተደጋግሟል። ይህም የሆነበት ምክንያት ኢየሱስ በመቃብር ውስጥ የሚቆይበት ጊዜ ብቻ ትኩረት እንዲሰጠው ለማድረግ ነው። ‹እንደ ዮናስ› የሚለው ቃል ‹ሙት ወይም ሕያው› ከሚለው ጋር በቀጥታ የሚገናኝ አይደለም» በማለትም ይከራከራሉ።

ኢየሱስ አጽንኦት የሰጠበት ጉዳይ የጊዜውን መመሳሰል እንደሆነ ለጊዜው እንቀበላቸው። ግን ከጊዜው አኳያ ትንቢቱ ተፈጽሞ እንደሆነ ዳግም እንጠይቅ። ክርስቲያኖች በቅጽበት የሚሰጡት መልስ አሁንም «እንዴታ!» የሚል ይሆናል።





## ዓውደ ዓመት

«ክርስቶስ መቼ ተሰቀለ?» የሚል ጥያቄ ይነሳል። የክረስቲያኑ ዓለም በጅምላ የሚሰጠው መልስ «ዓርብ» የሚል ይሆናል። ነጮች «መልካሙ ዓርብ» (Good Friday) በማለት የሚያከብሩት (በአገራችን ስቅለት ተብሎ የሚከበረው) ዓውደ ዓመት በደቡብ አፍሪካ የሕዝብ በዓል የተደረገበት ምክንያት ለዚህ ይሆን? ከአሜሪካ እስከ ዛምቢያ፥ ከኢትዮጵያ እስከ ዛየር ስቅለት በዓርብ ቀን ይከበራል። «መልካሙ ዓርብ»ን –ስቀለትን– ምን መልካም አደረገው? ተብለው ለሚቀርብላቸው ጥያቄ ክርስቲያኖች የሚሰጡት መልስ «የእኛን ኃጢአት ለማስተሰረይ ሲል ክርስቶስ በመስቀል ላይ የሞተበት ቀን ስለሆነ ነው» የሚል ይሆናል። ከ1950 ዓመታት በፊት ዓርብ ቀን ኢየሱስ በእርግጥ በመስቀል ላይ ተገድሏልን? ክርስቲያኖች ለእርግጠኝነቱ ሽንጣቸውን ገትረው ይከራከራሉ።

የወንጌልን አንቀጾች ረጋ ብለን ብንመረምር አይሁድ ኢየሱስን በፍጥነት ለማጥፋት ውክቢያ ላይ እንደነበሩ እንገነዘባለን። በጨለማ ያዙት። በመንፈቀ ሌሊት ለሊቀ ካህናቱ ፍርድ አቀረቡት። ሲነጋም ወደ ጲላጦስ ወስደው ይፈርድበት ዘንድ አሳልፈው ሰጡት። ጲላጦስ የሄሮድስ ግዛት ሰው መሆኑን ስለተረዳ ወደ ሄሮድስ ላከው። ሄሮድስ ደግሞ ወደ ጲላጦስ መለሰው። ኢየሱስን ለማስገደል የሚጣደፉት ሰዎች፥ሕዝቡ ከኢየሱስ ወግኖ በእነርሱ ላይ እንዳይነሳባቸው ስጋት ነበራቸው። ኢየሱስ የሕዝቡ ታላቅ ሰው ነበር። ብዙ ደጋግ ውለታዎችን ውሎላቸዋል። የኢየሱስ ጠላቶች ግን ሕዝቡን ውዥንብር ውስጥ አስገብተው በፍጥነት ሊያስወግዱት ተራወጡ። ይህም ተሳካላቸው። ኢየሱስን በመስቀል ላይ ለመስቀል የተጣደፉትን ያህል የዓርብ ጀንበር ከመጥለቋ በፊት ከመስቀሉ ላይ ለማውረድ ተዋክበው ነበር። ዓርብ ጀንበር ከምትጠልቅበት ቅጽበት ጀምሮ «ሰብት» (ቅዳሚት ሰንበት) ይጀምራል። በ«ሰብት» ቀን ደግሞ የተሰቀለን ሰው በመስቀል ላይ ማቆየት ኃጢአት እንደሆነ አይሁድ ያምናሉ። እንዲሁም በኦሪት ዘዳግም ላይ እንደተነገሩት በእንጨት ላይ የተሰቀለ በእግዚአብሔር የተረገመ ስለሆነ የእግዚአብሔርን ምድር እንዳያረክስ ቶሎ መቅበር ነበረባቸው።

«በእንጨትም ላይ ብትሰቅለው፥ በእንጨት ላይ የተሰቀለ በእግዚአብሔር ዘንድ የተረገመ ነውና! ሬሳው በእንጨት ላይ አይደር፤

ነገር ግን አምላክ እግዚአብሔር እርስት አድርጐ የሰጠህን ምድር እንዳታረክስ በእርግጥ በዚያ ቀን ቅበረው።» (ኦሪት ዘዳግም 21፥23)

የጸፎችና የፈሪሳውያን ሃይማኖታዊ ቀናኢነት በሚያረካና ተቃውሞ በማያስነሳ መልኩ ሁኔታዎች እንዲፈጸሙ ለማድረግ ቅድመ ዝግጅት ካጠናቀቁ በኋላ፥ ከኢየሱስ «ድብቅ ደቀ መዛሙርት» አንዱ፥ ቀኑ የቅዳሜ ሰንበት ዋዜማ መሆኑን በሽፋንነት ተጠቅሞ፥ የኢየሱስ ሥጋ እንዲሰጠው ጲላጦስን ጠየቀው። ፈቀደለት። የኢየሱስን አካል ከመስቀሉ ላይ አውርዶ ወሰደ። እነዚህ ደቀ መዛሙርት በአይሁድ ወግ መሠረት አጥበው፥ ገንዘውና ሽቶ ቀብተው ከመምሸቱ በፊት ቀበሩት። ስለዚህ ሁኔታ በዮሐንስ ወንጌል 19፥39–40 ላይ እንዲህ ይላል:- «ደግሞም አስቀድሞ በሌሊት ወደ ኢየሱስ መጥቶ የነበረ ኒቆዲሞስ መቶ ንጥር የሚያህል የከርቤና የእሬት ቅልቅል ይዞ መጣ። የኢየሱስንም ሥጋ ወስደው እንደ አይሁድ አገናነዝ ልማድ ከሽቱ ጋር በተልባ እግር ልብስ ከፈኑት።»

በአያሌ የክርስቲያን አንጃዎችን ክፍልፋዮች መካከል ያለው ልዩነት ግዙፍ ቢሆንም ከላይ በጠቀስኳቸው ነጥቦች ሁሉም በአንድነት ይስማማሉ። ኢየሱስ ዓርብ ምሽት በመቃብር ውስጥ እንደሆነ «ይገመታል»። ቅዳሜ ቀኑን በመቃ ብር ውስጥ እንደነበር «ይገመታል»። ቅዳሜ ሌሊትም እንዲሁ በመቃብር ውስጥ እንደነበር «ይገመታል»። ክርስቲያኖች በዚህ ጉዳይ ላይ ለመስማማት አያንገራግሩም።

«ይገመታል» የሚለውን ቃል ሦስት ጊዜ መደጋገሜን ያስተውሉ። ይህን ያደረግኩበት ምክንያት ወንጌሎቹ: ኢየሱስ ከመቃብር የወጣበትን እቅጩን ጊዜ ከመጠቆም ስለተቆጠቡ ነው። በጊዜው በዓርብ ዕለት ምሽት «ድብቅ ደቀ መዛሙርቱ» ለኢየሱስ ምቹና ተስማሚ እንደሆነ ወደሚገመቱት ሥፍራ ወስደ ውት ሊሆን ይችላል። ቢሆንም የወንጌል ጸሐፊያኑ በዝምታ ያለፉትን ጉዳይ እኔ የማንሳት መብት የለኝም። ስለሆነም «ይገመታል» የሚለውን ቃል ሦስት ጊዜ ደጋገምኩት።

በመጨረሻ ግን በትንቢቱ መሠረት በእርግጥ ሦስት ቀናትና ሦስት ሌሊቶች በመቃብር ውስጥ መኖር አለመኖሩን እንመርምር:-





| የፋሲካ ሳምንት | በመቃብር ውስጥ የቆየበት | |
|---|---|---|
| | ቀናት | ሌሊት |
| ዓርብ<br>ፀሐይ ከመጥለቋ በፊት ተቀብሯል | ምንም | አንድ ሌሊት |
| ቅዳሜ<br>በመቃብር ውስጥ እንደነበርይገመታል | አንድ ሙሉ ቀን | አንድ ሙሉ ሌሊት |
| እሁድ | ምንም | ምንም |
| አጠቃላይ ድምር | አንድ ሙሉ ቀን | ሁለት ሙሉ ሌሊቶች |

የቀንና የሌሊቶቹ አጠቃላይ ድምር አንድ ቀንና ሁለት ሌሊቶች እንጅ ሦስት ቀንና ሦስት ሌሊቶች እንዳልሆኑ ማስተዋላችሁን አልጠረጥርም። የክርስ ቲያኖቹን መጽሐፍ በመረጃነት ከተጠቀምን አሁንም ኢየሱስ ዳግም የቃሉን እንዳልፈጸመ እንገነዘባለን።

በመጀመሪያ:- ኢየሱስ «እንደ ዮናስ» ሕያው ወይስ «ከዮናስ በተቃራኒ ሙት» እንደሆነ ለማረጋገጥ የክርስቲያኖቹን መጽሐፍ እንመርምር። ኢየሱስ «እንደ ዮናስ» ሕያው ሆኖ ለተመሳሳይ ጊዜያት በምድር ልብ እንዳልኖረና «ሙት» እንደነበር እንገነዘባለን። ክርስቲያኖች የሚሉትን ከተቀበልን «እንደ ዮናስ» እያለ ትንቢት የተናገረውን የኢየሱስን ቃል እንቃረናለን። ኢየሱስ ትንቢቱንም እንዳልፈጸመ እናረጋግጣለን።

ሁለተኛ:-የስነ–መለኮት ሊቃውንቱ በጠቆሙን መሠረት ኢየሱስ በአጽን ኦት የተናገረው ምን ያህል ጊዜ በምድር ልብ እንደሚኖር ነው። በጀ! በማለት የጊዜውንም ጉዳይ አጠናነው ግን ይህም አልሆነም። ለሁለተኛ ጊዜ ኢየሱስ ትንቢቱን አጠፈ። የክርስቲያኑ ዓለም ታላላቅ የሒሳብ ሊቃውንት ሦስት ቀንና ሦስት ሌሊት ስንት ሰዓታት ሊሆኑ እንደሚችሉ ማስላት ተሳናቸው። በመሆኑም «የአንድ ቀንና ከሁለት ሌሊቶች ጋር እኩያ ናቸው» ሲሉ ፈረዱባቸው። 72 ሰዓታት ከ36 ሰዓታት ጋር እኩል አደረጓቸው። ወንጌሎች በግልጽ ከሚተር ኩልን በዕለተ ሰንበት ፀሐይ ከመውጣቷ በፊት መግደላዊት ማሪያም ወደ ኢየሱስ መቃብር ሄዳ መቃብሩን ባዶውን እንዳገኘችው እንረዳለን።

# «መልካም» ረቡዕ

የአርምስትሮንግ ቤተሰቦች መላው የክረስቲያን ዓለም ለዘመናት መሳሳቱን አስታወቁ። የሂሳብ ስሌቱን የደረሱበት ይመስላል። «ፕሌን ትሩዝ» (Plain Truth) መጽሔት አዘጋጅ የሆኑት ሚስተር ሮበርት ፋሂ (Mr. Robert Fahey) በቅርቡ ደርባን ውስጥ በ«ሆሊደይ ኢን» (Holiday Inn.) በተባለ ሆቴል ውስጥ ይህን ጉዳይ አስመልክተው ዲስኩር (Lecture) አስደምጠዋል። በቦታው እኔም ተገኝቻለሁ። ሚስተር ፋሂ ለክርስቲያን ታዳሚው ኢየሱስ ረቡዕ እንጅ ዓርብ ዕለት እንዳልተሰቀለ ለማስረዳት ይሞክራሉ። ለአለፉት ሁለት ሺህ ዓመታት ጥንታዊያቱ (ኦርቶዶክስ) ቤተ–ክርስቲያናት የስቅለት በዓልን ረቡዕ በማድረግ ፋንታ ዓርብ በማድረጋቸው ትልቅ ስህተት እንደፈጸሙ ለማሳየት መረጃዎችን ይደረድራሉ። እርሳቸው እንደሚነግሩን፥ አንድ ሰው ከእሁድ ጥዋት ጀምሮ ወደ ኋላ ሦስት ቀናትንና ሦስት ሌሊቶችን ቢቆጥር የሚያገኘው ቀን ረቡዕ ይሆናል። ስለዚህ ኢየሱስ የተሰቀለበትን ቀን በዚህ መልኩ ማስላት ይቻላል።

በመጀመሪያ ለሚስተር ፋሂ ብልኀንታቸውን እንደማደንቅ ገለጽኩላቸው። ከዚያም ለአለፉት ሁለት ሺህ ዓመታት መላው የክርስቲያኑ ዓለም የስቅለትን በዓል በረቡዕ ፈንታ በዓርብ ዕለት ሊያከብር እንደቻለ ግልጽ እንዲያደርጉልኝ ጠየቅኳቸው። በዓለማችን የሚገኘው ከ1200 ሚሊዮን የሚበልጥ የክርስትና ሃይማኖት ተከታይ ዛሬም ኢየሱስ ተሰቀለ የሚባልበትን ትክክለኛ ቀን አያውቅም። ከሐዋሪያው ጴጥሮስ ጀምሮ እስከ እኛ ዘመን ድረስ ያልተቋረጠ የሊቃነ ጳጳሳት ሰንሰለት እንዳላት በማወጅ የምትኩራራው የሮማ ካቶሊካዊት ቤተ ክርስቲያን እንኳ ይህን ቀን በትክክል ለማስቀመጥ ተስኗታል። በሚስተር ፋሂ ዲስኩር መሰረት ስህተት ላይ ወድቃለች።

## አምላክ ወይስ ሰይጣን?

በአያሌ ሚሊዮኖች የሚቆጠሩትን የክርስትና ሃይማኖት ተከታዮችን ለአለፉት ሁለት ሺህ ዓመታት ማን አታለላቸው የሚል ጥያቄ ይነሳል። አምላክ ወይስ ሰይጣን? ሚስተር ፋሂ «ሰይጣን!» በማለት ነበር ሳያቅማሙ የመለሱት።





«ሰይጣን፥ ክርስቲያኖችን ረቡዕ ወይም ዓርብ ስቅለትን ማክበር በመሳሰሉ ተራ የእምነታቸው ቅርንጫፎች ላይ ይህን ያህል ውዥንብር ውስጥ እንዲገቡ ማድረግ ከተሳካለት፥ፈጣሪን በተመለከተ መሠረታዊ የእምነታቸው ጉዳዮች ላይ ክርስቲያኖችን ማሳሳት ምን ያህል ቀላል እንደሚሆንለት ይታይዎታልን?» በማለት ጥያቄዬን ለሚስተር ፋሂ አቀረብኩላቸው። ፊታቸው በሃፍረትና በን ዴት የበርበሬ ድልኸ መሰለ። ወዲያውም ከእኔ ተለይተው ጉዞዋቸውን ቀጠሉ።

በዛሬይቱ ዓለማችን ጉዳዮች ላይ ከፍተኛ ሚና የሚጫወተው የክርስትና ሃይማኖት እምነት እንዲህ ከሆነ፥ አንድ ጥያቄ ኅሊናችንን ይጐተጉተዋል። ይህ ሁኔታ በታሪክ ውስጥ ወደር የማይገኝለት ታላቅ ማጭበርበር እንደተፈጸመ አመልካች ሊሆን አይችልምን?

ክፍል ሦስት

# ትንሣኤ ወይስ ማንሰራራት?

አስተውሎታቸው እንዲዛባና እንደተነገራቸው ብቻ እንዲያስቡ የተደረጉ የዋህ አማንያንን ጉዳይ ትኩረት ሰጥቼ ለማጥናት ቃል ገብቻለሁ። የሚከተለውን የሕይወት ገጠመኜን እተርክላችኋለሁ። በአቅራቢያዬ የሚገኙ ክርስቲያኖች የበሰለና የነጠረ የእንግሊዝኛ ችሎታ አላቸው። ሆኖም ግን የሚያነቡትን ነገር በፍጹም የሚቃረን ግንዛቤ እንዲያዳብሩ በጥንቃቄ በተቀነባበረ ፕሮግራም ውስጥ አልፈዋል። ገጠመኜ ይህንን ጉዳይና «ትንሣኤ ወይስ ማንሰራራት» በሚል አብይ ርዕስ የማቀርበውን መጣጥፍ ያብራራልኛል።

ወደ ትራንስቫል ክፍለ ሀገር ሄጄ ትምህርታዊ ዲስኩር (Lecture) ለማስደመጥ በዝግጅት ላይ ነኝ። በስታንዳርተን ከተማ ውስጥ ሀፊዝ ዩሱፍ ዳዱ የሚባል ጓደኛዬ ይኖራል። ስልክ በመደወል ወደሱ ለመሄድ ዝግጅቴን እንዳጠናቀቅኩ አስታወቅኩት። ከደርባን ከተማ እንዳመጣለት የሚፈልገው ነገር ካለ እንዲጠቁመኝ ጠየኩት። የእብራይስጥ ቋንቋ እያጠና እንደሆነ ገለጸልኝ። ቀጥሎም በእብራይስጥ ቋንቋ የተጻፈና ጐን በጐን እንግሊዝኛ ትርጉሙን የሚያስቀምጥ መጽሐፍ ቅዱስ እንዳመጣለት ጠየቀኝ።

በደርባን ውስጥ ወደሚገኘው «ዘ ባይብል ሀውስ» ወደሚባል የመጽሐፍ ቅዱስ መደብር አመራሁ። ጓደኛዬ እንዳመጣለት የጠየቀኝን መጽሐፍ ካለ አንዳች ችግር አገኘሁት። «የተፈቀደ ቅጅ» (Authorized Version) ወይም በሌላ አባባል «የንጉሥ ጀምስ ቅጅ» (King James Version) የሚባለውን መጽሐፍ አነሳሁ። የተሻለ ሕትመትና የዋጋ ቅናሽ ያለውን ጥራዝ ማማረጥ ጀመርኩ። ቀና ብዬ ስመለከት ከገንዘብ መቀበያው ሳጥን ውስጥ የተቀመጠችው ሴት የስልክ መነጋገሪያውን (የጥሪ መቀበያውን) አንስታ ከአንድ ሰው ጋር እየተነጋገረች መሆኑን አስተዋልኩ።ንግግሯን በማዳምጥበት ርቀት ላይ አልነበርኩም። ፍላጐቱም አልነበረኝም። ከስልኩ የሌላኛው መስመር የሚመጣውን ድምጽ ካዳመጠች በኋላ፥ እጇን ከመነጋገሪያው አፍ ላይ አስቀመጠች። ወደ እኔ በመጣራት «ይቅርታ የኔ ጌታ ሚስተር ዲዳት የሚባሉት እርስዎ አይደሉ ምን? » በማለት ጠየቀችኝ። «አዎ፥ እኔ ነኝ» በማለት መለስኩላት። «የመጽሐፍ ቅዱስ ማኅበር ተቆጣጣሪ (Supervisor)ሊያነጋግሩዎት ይፈልጋሉ» አለችኝ። «ደስ ይለኛል» አልኳት። እጇን ከስልኩ ላይ መልሳ፥ጥቂት





ቃላቶችን ከተነጋገረች በኋላ የጥሪ መቀበያውን ወደ ስልኩ ቀፎ መለሰችው። «እኔ ደግሞ ፖሊስ እየጠራሽ መስሎኝ ነበር» በማለት ፈገግ አልኩ። ሳቀች። «በፍጹም እንደዚያ አላደርግም። ክቡር ቄስ ሮበርትስ (ሬቨረንድ ሮበርትስ) እርስዎን ማነጋገር ስለሚፈልጉ ይህንኑ ሁኔታ ለማመቻቸት ነው የደወልኩላቸው።»

## ለማጥመቅ መቋመጥ

ሬቨረንድ ሮበርትስ መጡ። ወደ እኔ በመቅረብ ራሳቸውን አስተዋወቁኝ። በእጄ ይገኘው የነበረውን መጽሐፍ ቅዱስ እንድሰጣቸው በምልክት ጠቆሙኝ። መጽሐፉን ሰጠኋቸው። መጽሐፉን ገልጠው ከዮሐንስ ወንጌል ከምዕራፍ 17 አንቀጽ 3 የሚከተለውን ማንበብ ጀመሩ። «እውነተኛ አምላክ ብቻ የሆንህ አንተን የላክኸውንም ኢየሱስ ክርስቶስን ያውቁ ዘንድ ይህች የዘላለም ሕይወት ናት።» (እርሳቸው ይህን ሲናገሩ እኔ ደግሞ የጠቀሱት አንቀጽ ከወንጌል አንጻር ትክክለኛነት እንዳለው አረጋገጥኩኝ።)

ከመጽሐፉ ያነበቡልኝን አንቀጽ ካዳመጥኩ በኋላ «ያነበቡልኝን አንቀጽ እቀበለዋለሁ።» አልኩ። ይህን ስል ለእኔ ማስተላለፍ የፈለጉት መልዕክት ትርጉም ገብቶኛል ለማለት ነው። እርሳቸው ሊያስተላልፉልኝ የሞከሩትን መልዕክት ጭብጥ ቅዱስ ቁርአን ለአለፉት ዐሥራ አራት መቶ ዓመታት ሲያስተምረው እንደነበር ግን አልገለጽኩላቸውም። ሙስሊሞች ሁሉ በአንድና ብቸኛ በሆነ ፍጹም ፈጣሪ፥ እንዲሁም በኢየሱስ የአምላክ መልክተኝነት ማመን አለባቸው። የቅዱስ ቁርአንን ቃላት ለመጠቀም:-

> «የመርየም ልጅ አልመሲሕ ዒሳ የአላህ መልክተኛ፥
> ወደ መርየም የጣላት (የኹን) ቃሉም ከርሱ የኾነ መንፈስም
> ብቻ ነው፤ በአላህና በመልክተኞቹም እመኑ፤ »
>
> (አል–ኒሳእ፥171)

ሬቨሬንድ ሮበርትስ ከመጽሐፍ ቅዱስ ለጠቀሱት ጥቅስ «እቀበለዋለሁ» የሚል አዎንታዊ ምላሽ በማግኘታቸው መፈንደቃቸውን ሁኔታቸው ይናገራል። መጽሐፉን በፍጥነት ገልበጥ ገልበጥ በማድረግ ሌላ ቦታ ገለጡ። ቀጥሎ የሚመለከተውን ኢየሱስ ተናግሮታል የሚባልለትን አንቀጽ አነበቡልኝ:-

«እርስ በርሳችሁ ትዋደዱ ዘንድ፥ እንደ ወደድኋችሁ እናንተ ደግሞ እርስ በርሳችሁ ትዋደዱ ዘንድ አዲስ ትእዛዝ እሰጣችኋለሁ። እርስ በርሳችሁ ፍቅር ቢኖራችሁ ደቀ መዛሙርቴ እንደሆናችሁ ሰዎች ሁሉ በዚህ ያውቃሉ።» (ዮሐንስ 13፥34–35)

## አዲስ አማኒ

እነዚህን አንቀጾች አነብንበው ሲጨርሱ፥ «በጣም ጥሩ» የሚል አስተያየት ሰጠሁ። ይህ አስተያየት እጅግ አበረታታቸው። አስተያየቴን የሰጠሁት በቅንነት ከልቤ እንጅ ለማስመሰል አልነበረም። ሬቨረንዱ አሁንም መጽሐፉን ገልበጥ አድርገው ሌላ ጥቅስ አገኙ። ክርስቶስን የሚቀበል አዲስ አማኒ አጥምደው በመያዛቸው ሊለቁት አልፈለጉም። ማንበብ ጀመሩ:-

«እንዳይፈረድባችሁ አትፍረዱ፤በምትፈርዱበት ፍርድ ይፈረድ ባችኋልና፥በምትሰፍሩበትም መስፈሪያ ይሰፈርባችኋል።» (ማቴዎስ 7፥1–2)

ለዚህ ጥቅስ የሰጠሁት ምላሽ፥ «እስማማለሁ» የሚል ነው። እርሳቸው ለሚጠቅሷቸው ጥቅሶች «እስማማለሁ» ወይም «እቀበላለሁ» የሚል ምላሽ የምሰጠው የቅዱስ መጽሐፍ ማኅበሩ ስለደንበኝነቴ በተደጋጋሚ ያደርግልኝ ስለነበረው «ልዩ የዋጋ ቅናሽ» ውለታ ቢጤ ለመስራት አልነበረም። የእነዚህ ጥቅሶች የሚያስተላልፉት መሠረታዊ መልክትና ዓላማ አላህ (ሱ.ወ) ሙስሊሞች እንዲያስተምሩና በገቢር እንዲያውሉ ካዘዛቸው መልክት ጋር ተመሳሳይነት እንዳለው እያወቅኩ በጭፍን ጥላቻ ብቻ ተነሳስቼ ሬቨረንዱ የሚናገሩትን መቃወም የሚዋጥልኝ አይደለም። ሙስሊሞችና ክርስቲያኖች በጋራ የሚያስተላልፏቸውን አስተምህሮቶች እንዳላቸው ሁሉ፥ በፍጹም የማይስማሙባቸው አያሌ ነጥቦች እንዳሉ ጠንቅቄ አውቃለሁ።

ከቅዱስ ቁርኣን የተወሰደ አንድ መልክት እጹብ ድንቅ እንደሆነ ስናገር፥ በሌላ ወገን፥ ያው መልክት በመጽሐፍ ቅዱስ አማካኝነት ሲነገረኝ እርኩስ እንደሆነ ማስታወቅ የለየለት ግብዝነትና ጭፍንነት እንደሆነ ይሰማኛል። ጎሊናን የሚቆጠቁጥ እብለት ይመስለኛል።





## የሬቨረንዱ ዓላማ

ሬቨረንዱ እኔ ፊት መጽሐፍ ቅዱስን ማነብነብ ያነገበው ዓላማ ምን ይሆን? በእርግጥ የመጽሐፍ ቅዱስ ማኅበር በምገዛቸው ዕቃዎች ላይ የተለየ የዋጋ ቅናሽ ሲያደርግልኝ ቆይቷል። ምናልባትም እንዲህ ዓይነቱን የዋጋ ቅናሽ በማግኘት ረገድ ብቸኛው ክርስቲያን ያልሆነ ሰው ነኝ ማለት እችላለሁ። ቄሱ የመጽሐፍ ቅዱስ ማኅበር ፕሬዚዳንት እንደመሆናቸው መጠን ለኔ ስለሚደረግልኝ የዋጋ ቅናሽ ሳይነገራቸው የቀረ አይመስለኝም። አለባበሴ፥ በራሴ ላይ የደፋሁት ኮፍያ እንዲሁም የተኰ ጐደጐደው ጢሜ ሙስሊምነቴን የሚያሳውቁ ምልክቶች ናቸው። በእንግሊዝኛ፥ በዙሉ፥ በአፍሪካንስ፥ በኡርዱ፥ በዓረብኛና በተለያዩ ሌሎች ቋንቋ የተዘጋጁትን ቅዱሳን መጻሕፍት በመግዛት ረገድ እታወቃለሁ። ስለሆነም ይህን ከግምት አስገብተው ቄሱ እኔን በዝግታ እየገፉ ክርስትና እርከን ላይ ሊያወጡኝ መሠረታዊ ዓላማቸው ነበር። የመጽሐፍ ቅዱሱም ንባብ ከዚሁ ዓላማ የመነጨ ነው። ከመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የጠቃቀሷቸውን እንያን ውብ አንቀጾች ቀደም ሲል የማውቃቸው ስለመሆኔ ቄሱ የተረዱት ዘግይተው ነበር። ይህ ከሆነ የኔን ክርስትናን እስከ ዛሬ ሳልቀበል መቅረቴ ጉድ ሳያሰኛቸው የቀረ አልመሰለኝም።

## አንድ ችግር

ሬቨረንዱ ለማስተማር ጉጉት እንዳለው መልካም መምህር ዓይነት ናቸው። ያላቸውን ዕውቀት ለተማሪያቸው ለማካፈል ይታትራሉ።

እኔም እንደ መልካም ተማሪ በተመስጦ አዳምጣቸዋለሁ። ሙስሊሞች፥ ነቢዩ ሙሐመድ (ሶ.ዐ.ወ) ያስተማሩንን «(በእናታችሁ) እቅፍ ውስጥ ከነበራ ችሁበት (የህፃንነት) ጊዜ ጀምሮ የመቃብር ዐፈር አስኪጫናችሁ ድረስ ዕውቀትን ፈልጉ» የሚለውን ትእዛዝ፥ እንዲሁም «ቻይና ድረስ እንኳ ቢሆን በመጓዝ ዕውቀትን ፈልጉ» የሚለውን ነቢያዊ መመሪያ ተግባራዊ አደረግኩ። ትምህርታቸውን በዚህ መንፈስ ተከታተልኳቸው። «ለእኔ ባነበቡልኝ አናቅጽ በሙሉ እስማማለሁ። ግን በመጽሐፋችሁ ውስጥ አንድ ችግር ይታየኛል» ስል ቅሬታየን ገለጽኩላቸው። «መጽሐፋችን ውስጥ ምን ችግር አገኘህበት? » ሲሉ ጠየቁኝ። «እባክዎን የሉቃስ ወንጌል ምዕራፍ 3 አንቀጽ 23 ይግለጡ» አልኳቸው። ገለጡ። እንዲያነቡልኝ ጠየቅኳቸው። እንደሚከተለው አነበቡት:-

«And Jesus Himself began to be about thirty years of age, being (as was supposed) the Son of Joseph, which was the Son of heli,» (Luke 3፥23)

«ኢየሱስም ሊያስተምር ሲጀምር ዕድሜው ሰላሳ ዓመት ያህል ሆኖት ነበር፤ እንደ መሰላቸው የዮሴፍ ልጅ ሆኖ፥ የኤሊ ልጅ፥» (ሉቃስ 3፥23)

(እዚህ ላይ የእንግሊዝኛውን መጽሐፍ ቅዱስ እንዳለ ማስቀመጥ ያስፈለገኝ «(as was supposed)» የሚሉትን ቃላት የእንግሊዝኛው መጽሐፍ ቅዱስ በቅንፍ ውስጥ ያስገባቸው መሆኑን ለማመልከት ነው። የቃላቱ አማርኛ ትርጉም «እንደ መሰላቸው» የሚለው ሲሆን፥ ወደ አማርኛ መጽሐፍ ቅዱስን የመለሱት ሰዎች ቅንፉን ረስተውታል። አለያም ሆን ብለው አውጥተውታል። የዚህ ጽሑፍ ባለቤትና ሬቨረንዱ የሚወያዩት በቅንፉ ጉዳይ ላይ ስለሆነ የአማርኛው መጽሐፍ ቅዱስ ብዙም አይረዳም።) (ተርጓሚው)

የሬቨረንዱ አትኩሮት «እንደ መሰላቸው»፥ "(as was supposed)" ወደ ሚሉት ቃላት እንዲያነጣጥር አደረኩ። እንዲህ ስል ጠየኩዋቸው:- «as was supposed» የሚሉት ቃላት በቅንፍ ውስጥ እንደተቀመጡ አስተውለዋልን?»፥ እንደተመለከቷቸው ገለጹልኝ። «ለምን ቅንፎቹን መጠቀም አስፈለገ?» በማለት ጠየኩዋቸው። «እኔ እንኳ ለምን እንደተቀመጡ አላውቅም። ግን የመጽሐፍ ቅዱስ ሊቃውንትን አነጋግሬ ምክንያቱን አስረዳዎታለሁ።» አሉኝ– ሬቨረንዱ። ትሕትናቸውን አደነቅኩ። ምንም እንኳ የመጽሐፍ ቅዱስ ማኅበራት ሱፐርፋይዘርነት በመጽሐፍ ቅዱስ በዕውቀታቸው የበሰሉ ሬቨረንዶች (ቀሳውስት) ጡረታ ሲወጡ የሚሰጣቸው የማዕረግ ቦታ እንደሆነ ባውቅም፥ እንደዚህ ዓይነቱ የመጽሐፍ ቅዱስ ዕውቀት ከችሎታቸው በላይ ሊሆን እንደሚችል ገመትኩ። «እርስዎ ግልጽ ካልሆነልዎ፥ በዚህ አንቀጽ ውስጥ ያለውን ቅንፍ ለምን ማስቀመጥ እንዳስፈለገ ላስረዳዎ እሞክራለሁ። ወደ መጸሐፍ ቅዱስ ሊቃውንቶች ለመሄድ አይቸገሩ።»

«እጅግ በጣም ጥንታዊ» እንደሆኑ በሚነገርላቸው የሉቃስ ወንጌል ቅጅ በተጻፈባቸው መረጃዎች (ዶክሜንቶች) ውስጥ «እንደ መሰላቸው»–(«as was supposed») የሚሉ ቃላቶች የሉም። ነገር ግን ተርጓሚዎቻችሁ እንደዚህ





ዓይነት ማብራሪያ ካላስቀመጡ ለሃይማኖቱ ጥልቅ ዕውቀትና እምነት የሌለው ሕዝብ ስህተት ላይ እንዳይወድቅ ሰጉ። ኢየሱስን የጠራቢው የዮሴፍ የአብራኩ ክፋይ የሆነ የስጋ ልጁ እንደሆነ አድርገው ይወስዱታል ብለው አመኑ። ይህን ችግር ለማስወገድ በቅንፍ ውስጥ የራሳቸውን አስተያየት በማከል የሕዝቡ ግንዛቤ እንዳይዛባ ጣሩ። «እኔ አንባቢውን ለመርዳት አስባችሁ በቅንፍ ውስጥ የራሳችሁን ማብራሪያ የማስፈር ሥልታችሁ መጥፎ እንደሆነ አላምንም። ሆኖም ግን መጽሐፍ ቅዱስን ወደ ተለያዩ የአፍሪካና የምሥራቁ ዓለም ቋንቋዎች ስትተረጉሙ–«as was supposed»–«እንደ መሰላቸው»–የሚሉትን እናንተ የጨመራችኋቸውን ቃላት ከቅንፍ ውስጥ በማውጣት የዋናው መጽሐፍ አካል በማስመሰል እንዳሉ በማስቀመጣችሁ ቅሬታ ገብቶኛል። ከእናንተ (ከእንግሊዝኛ ተናጋሪ) ውጭ ያሉ ሕዝቦች የቅንፉን ትርጉምና ዓላማ አይረዱም ብላችሁ ትጠራጠራላችሁን?

ለምን ከአፍሪካነሮች መጽሐፍ ቅዱስ ላይ ቅንፎች ተወገዱ? አፍሪካነሮች ምን ችግር አለባቸው ብላችሁ ታስባላችሁ?»

«እንዴ! እኔ እኮ አላደረግኩትም» በማለት የተቃውሞ ድምጽ አሰሙ። «እርስዎ በግለሰብ ደረጃ የጨመሩት ወይም የቀነሱት ነገር እንደሌለ አውቃለሁ። ግን እርስዎ የሚወክሉት የመጽሐፍ ቅዱስ ማኅበርና የመጽሐፍ ቅዱስ ሊቃውንቶቻችሁ ለምንድን «በእግዚአብሔር ቃል» ላይ እንዳሻቸው ይጫወታሉ?! ሁሉን ቻይ የሆነው እግዚአብሔር ሉቃስን ከስህተት መጠበቅ አላስፈላጊ ሆኖ ካገኘውና የጻፈውን እንዲጽፍ በራዕይ ከረዳው «ከእግዚአብሔር መጽሐፍ» ላይ ቃላትን የመጨመር ወይም የመቀነስ መብት ማን ሰጣችሁ? «የእግዚአብሔርን ቃላት» ለመፈብረክ ማን ፈቀደላችሁ?»

## ብረዛዎች

ተርጓሚዎች የራሳቸውን ቃላት በቅንፍ ውስጥ በማድረግ ጨምረዋል። እነዚህን ቃላት እግዚአብሔር በቅዱስ ሉቃስ አንደበት ላይ ማስቀመጥ ቢፈልግ ኖሮ ማስቀመጥ ይችል ነበር። ሉቃስ ደግሞ በእግዚአብሔር ራዕይ እየተረዳ የሚጽፍ ከሆነ፥ አምላክ በመጽሐፉ እንዲካተቱ የሚፈልጋቸውን ቃላት ስለሚከትብ የሰዎች ብረዛ አያስፈልግም። ምክንያቱም ሰዎች ለትክክለኛ ግንዛቤ ብለው የሚቀንሷቸውና የሚጨመሯቸው ነገሮች በኦፊሴል «የአምላክ ቃላት» ሆነው ይሰፍራሉ። ቅንፎችም አስፈላጊ አይሆኑም። (ለተጨማሪ መረጃ «Is

The Bible God's word?» የሚለውን ጽሑፍ ይመልከቱ።) «የሥነ-መለኮት ሊቃውንቶቻችሁ ለጥንታዊያኑ አልኬሚስቶች ያልተሳካላቸውን ተራ ብረትን ወደ አንጸባራቂ ወርቅ የመለወጥ ጥረት እናንተ ተሳክቶላችኋል» በማለት ማብራሪያዬን ቋጨሁ።

## የእንግሊዝኛ ቋንቋ

ይህኔ ሬቨረንዱ የትኩረት አቅጣጫችንን ለማስቀየር በጭውውታችን መሃል አላስፈላጊ ዝባዝንኬ እያነሱ መተረክ ጀመሩ። ስንወያይበት የነበረው ጉዳይ ወደ ሌላ አቅጣጫ ተቀየረ። የተለያዩ ጉዳዮችን እያነሳን እየተወያየን ሳለን፥ ከመጽሐፍ ቅዱስ እየጠቀሱ የሚሰጡኝ ማብራሪያ መናገር የፈለግኩትን ነገር እንድናገር ገፋፉኝ።

● «ክቡርነትዎ ሆይ! እናንተ የእንግሊዝኛ ተናጋሪ ሕዝቦች ቋንቋችሁን እንኳ በቅጡ የምታውቁ አይደላችሁም» አልኳቸው።

(የአፍ መፍቻ ቋንቋቸው እንግሊዝኛ ለሆነ አንባቢያን ይቅርታ እጠይቃለሁ።)

●● «የእኔን ቋንቋ ከእኔ በላቀ ሁኔታ እንደሚያውቁት ሊያስታውቁኝ ይፈልጋሉን?» አሉ ሬቨረንዱ ቆጣ እና ፈጠን ብለው።

● «በእርግጥ ለአንድ እንግሊዝኛ ተናጋሪ፥የእርሱን ቋንቋ ከእርሱ በተሻለ ሁኔታ እንደምትረዳው መግለጽ ግነት ያለበት ይመስላል» አልኩኝ።

●● «ታዲያ፥ እኛን የእንግሊዝኛ ተናጋሪ ሕዝቦች ቋንቋችን ን እንኳ በቅጡ መረዳት እንደተሳነን ሲናገሩ ምን ለማለት አስበው ነው?»

● «ክቡርነትዎ ሆይ! እስኪ ለአንድ አፍታ ያስተውሉ። መጽሐፍ ቅዱሳችሁን በእናታችሁ ቋንቋ ታነባላችሁ የምትረዱት ግን ከምታነቡት እውነታ በተቃራኒ ነው። ይህ ችግር በእርግጥ በእናንተ ብቻ የተወሰነ አይደለም። የተለያዩ ቋንቋዎች የሚናገሩ ክርስቲያኖች በቋንቋቸው መጽሐፍ ቅዱስ ቢቀርብላቸውም የሚያነቡትና የሚረዱት አራምባና ቆቦ ነው።





●● «ምን ለማለት እንደፈለጉ ቢገልጹልኝ?» ሬቨረንዱ ጠየቁ።

## መንፈስ

● ንግግሬን ቀጠልኩ፥ «ኢየሱስ ተሰቀለ ከተባለ በኋላ ሐዋሪያቱ ወደተሰበሰቡበት ወደ ላይኛው ክፍል መምጣቱን ያስታውሳሉ? ‹ሰላም ለእናንተ ይሁን› አላቸው።ነገር ግን ደነገጡና ፈሩ።መንፈስም ያዩ መሰላቸው።(ሉቃስ 24፥36)፤፤ሐዋሪያቱ ኢየሱስን ባዩበት ቅጽበት ምን ያህል እንደተረበሹ አስተውለዋልን?» ትዕይንቱን በደንብ እንደ ሚያስታውሱት ገለጹልኝ። «ግን ያን ያህል ለምን ደነገጡ?» ጠየቅ ኳቸው። «እርስዎም እንደሚረዱት አንድ ሰው ለረጅም ጊዜ የተለዩ ውን የቅርብ ጓደኛውን ወይም ወዳጁን ሲያገኝ እጅግ በጣም ተደስቶ፥ ልቡ የእርካታ ደም እየረጨችና እየዘለለች ወዳጁን ለማቀፍ፥ እጆቹንና እግሮ ቹን ለመሳም አፈፍ ብሎ ይነሳል። ግን እነሱ ተደናገጡ፥ ፈሩ። ለምን?»

●● «(ሐዋሪያቱ) መንፈስ ያዩ ስለመሰላቸው ነው የተደናገጡት» ሬቨረንዱ መለሱ።

● «ኢየሱስ መንፈስ ይመስላልን?» ጠየኳቸው።

●● «እንዲያውም» አሉኝ።

● «ታዲያ መንፈስ ካልመሰለ እርሱን ሲያዩ ለምን መንፈስ ይሆ ናል የሚል ሐሳብ ብልጭ አለባቸው?»

●● የሬቨረንዱ ጭንቀት ከፊታቸው በጉልህ ይነበ ባል። «እንዳብራራለዎ ይፍቀዱልኝ» አልኳቸው።

## ደቀ መዛሙርቱ የዓይን ምስክር አልነበሩም

●«ክቡርነትዎ እየተከተሉኝ ነው? ቅዱስ ማርቆስ እንደሚያረጋ ግጥልን የኢየሱስ ደቀመዛሙርት የዓይንም ሆነ የጆሮ ምስክሮች አልነ በሩም። ይህ ድርጊት በተፈጸመበት በአለፉት ሦስት ቀናት ውስጥ ኢየሱስን ትተውት ጠፍተዋል። ‹ሁሉም ትተውት ሸሹ› (ማርቆስ

14፥50)። ደቀመዛሙርቱ ስለ መምህራቸው ያላቸው ዕውቀት ሁሉ የመነጨው በአካባቢው ተነዝቶ ከነበረው አሉቧልታ ነው። መምህራቸው በመስቀል ላይ እንደተሰቀለ ተነግሯቸዋል። መንፈስ እንደራቀው ወሬ ደርሷቸዋል። ሞቶ ለሦስት ቀናትና ለሦስት ሌሊቶች እንደተ ቀበረ ሰምተዋል። ተባራሪ ወሬ ጆሯቸውን አደንቁሯቸው፥ የኢየሱስን መሞት ተረድተው እርማቸውን ያወጡት ደቀመዛሙርት፥ አሁን ድንገት ሳያስቡት እፊታቸው ድቅን ያለው ምስል ቢያስደነብራቸው አይደንቅም። እነዚህ ዐሥር ደቀመዛሙርት ፊት ለፊታቸው ቆሞ የሚያዩት የኢየሱስ አካል ምናልባት የሙት መንፈሱ እንደሆነ ብለው ተጨነቁ።

«ኢየሱስ መረበሻቸውን አስተዋለ። አዕምሯቸውን ጨምድዶ ከያዛቸው ፍርሃት ሊያላቅቃቸው አሰበ። እሱ ራሱ መሆኑን እንዲገነዘቡ ለማድረግ ቀስ ብሎ ማግባባት ጀመረ። ‹ስለምን ትደነግጣላችሁ? ስለ ምንስ አሳብ በልባችሁ ይነሳል? እኔ ራሴ እንደሆንሁ እጆቼንና እግሮቼን እዩ፤ በእኔ እንደምታዩት መንፈስ፥ ስጋና አጥንት የለውምና እኔን ዳስሳችሁ እዩ አላቸው።› (ሉቃስ 24፥39)»

«በሌላ አባባል ‹ወዳጆቼ ምን ነካችሁ? ከእናንተ ጋር ስጫወት፥ ስንዝና ዳቦ ስቆርስ የነበርኩ እንደናተው ደምና ስጋ ለባሽ ፍጡር አይደ ለሁምን? ጥርጣሬ እንዴት በልቦናችሁ ውስጥ ልታሳድሩ ቻላችሁ? እንደምታዩት እንደ ማናችሁም አጥንትና ሥጋ ያለኝ ሰው ነኝ። የሙት መንፈስ ወይም ሌላ አይነት በእጅ የማይዳሰሱት ፍጡር አይደለሁም› በማለት ሊያረጋጋቸው መሞከሩ ነው።»

●የተለዬ ሐሳብ እንዳላቸው ለማረጋገጥ «እንደዚያ አይደለምን?» በማለት ሬቨረንዱን ጠየቅኳቸው።

●● «እንደዚሁ ነው» በማለት መለሱልኝ።

ውይይቱን ቀጠልን። ከሉቃስ ወንጌል 24፥39 እንደምንረዳው ኢየሱስ በማያሻማ ቋንቋ ማንነቱን ገልጾላቸዋል። እጆቼንና እግሮቼን ዳስሰው ወደ ሌላ የተለወጠ አካል እንዳልሆን እንዲያረጋግጡ ጠየቃቸው። ከሙት የተነሳ አካልም እንዳልሆነ እንዲያስተውሉ አበረታታቸው። ምክንያቱም ከሙት የተነሳ አካል ወደ መንፈስነት ይለወጣል። እርሱ ግን አልተለወጠም። በግልጽ ቋንቋ እነሱ





እንደሚያስቡት ከሙታን ዓለም አምልጦ የመጣ መንፈስ አለመሆኑን ነገራቸው። የእነሱ ጥርጣሬ ከንቱ እንደሆነና እርሱ ግን ያው የሚያውቁት ኢየሱስ እንደሆነ አስረዳቸው።

## ወደ መንፈስነት መለወጥ

እዚህ ላይ ጥያቄ አለኝ። «ከሞተ በኋላ የተነሳ አካል በኢየሱስ ትንሣኤ በግልጽ እንደተስተዋለው ስጋና አጥንት ለባሽ የማይሆንበት ምክንያት ምንድን ነው? እርስዎ ከምን ተነስተው ነው እንዲህ የሚናገሩት?» ሬቨረንዱ አጉተመተሙ። «ከሞት የተነሳ አካል ወደ መንፈስነት እንደሚለወጥ ማስረጃዬ የኢየሱስ ንግግር ነው» አሉኝ።

●●«እንደዚህ ዓይነት ንግግር መቼ ነው የተናገረው?» ሬቨረንዱ ጠየቁ።

● «በሉቃስ ወንጌል ምዕራፍ 20 የሰፈረውን ታሪክ ያስታውሳሉን? የካህናት አለቆችና ጻፎች በተንኰል ሊያጠምዱት ቋመጡ። ለወጥመዳቸው የሚያመቻቸውን ጥያቄዎች አዘጋጁ። ከጥያቄዎቻቸውም መካከል የአንዲት አይሁድ ሴት ጉዳይ ነበረበት። ሴትዮዋ በተከታታይ ሰባት ወንድማማቾች አገባች– አንዱ ሲሞት ሌላው እያገባት። ይህ የአይሁድ ወግ ነበር። ሰባቱ ባሎች ከሞቱ በኋላ እርሷም ተከተለች።

ሬቨረንዱ ሁኔታውን እንዳስታወሱት ገለጹልኝ። ሸማቂዎቹ በትህትና መረባቸውን ዘረጉ። «ይህችን ሴት በትንሣኤ ቀን ማን ሊያገባት ነው? ሰባቱም አግብተዋታል። ሁሉም ዳግም ሊያገቧት ይጓጉ ይሆናል። ሁሉም ከእርሷ ዘር ለማስቀረት የተቻላቸውን ሁሉ አድርገዋል– አንዱ ሲሞት ሌላው እየተተካ። በትንሣኤ ቀን ሰባቱም ሕያው ይሆናሉ። በገነት ውዝግብ ይነሳል። እርሷን ለመውሰድ ከሁሉም የበለጠ መብት ያለው የትኛው ነው?»

«ኢየሱስ ሴራቸውን አወቀባቸው። ስለ ትንሣኤ ያላቸውን የተሳሳተ ግንዛቤም በማጋለጥ አሳፈራቸው። ከትንሣኤ ቀን በኋላ ‹ሊሞቱ ወደ ፊት አይቻላቸውም።› (ሉቃስ 20፥35)። ይህንን የተናገረው ከሞት የተነሱ ሰዎች በፍጹም ሞትን የማይቀምሱ ይሆናሉ በማለት ነው። እነዚህ ሰዎች ከትንሣኤ ጀምሮ አይሞቱም፥ አይራቡም፥ አይጠሙም። እንዲሁም አይታክቱም። በሌላ አባባል ሰዎችን ለሞት የሚያበቋቸው ምክንያቶች ሁሉ ከሞት በተነሳ አካል ላይ ኃይል አልባ ይሆናሉ። ኢየሱስስም በመቀጠል ምክንያቱን ሲያብራራ ‹እንደ

መላእክት ናቸውና› ብሏል። ወደ መላእክነት – ወደ መንፈስነት– ተቀይረዋል። የመንፈስ ፍጡራን ይሆናሉ። እነዚህ «የትንሣኤ ልጆች ስለሆኑ የእግዚአብሔር ልጆች ናቸው።» (ሉቃስ 20፥36)

## ኢየሱስ ወደ መንፈስነት አልተለወጠም

መጀመሪያ ላብራራ ከተነሳሁት አብይ ነጥብ ወጥቼ ወደ ሌላ ጉዳይ እንድገባ ያደረገኝ የሬቨረንዱ «እንዴት እርግጠኛ ልትሆን ትችላለህ?» የሚለው ጥያቄ ነው። ወደ አብይ ነጥቡ እመለሳለሁ። ኢየሱስ ደቀመዛሙርቱ እንደገመቱት ወደ መንፈስ የተቀየረ አካል፥ የሙት መንፈስ ወይም ሊዳሰስና ሊጨበጥ የማይችል አካል አልነበረም። እጁንና እግሩን በእጃቸው ዳሰው እሱ ራሱ እንጅ ያልተለወጠ መሆኑን፥ ቀደም ሲል እንደሚያውቁት አጥንትና ስጋ የለበሰ ሰው እንጅ ሌላ እንዳልሆነ እንዲያረጋግጡ አደረገ። የእነሱ ጭንቀትና ፍርሃት ሁሉ መሠረተ–ቢስ እንደሆነ አስረዳቸው። የሚነግራቸው ነገር እውነትነት እንዳይጠራጠሩ ለማድረግ ምግብ ካላቸው እንዲሰጡት ጠየቀ።

«በዚህ አንዳች የሚበላ አላችሁን? አላቸው። እነሱም ከተጠበሰ ዓሣ አንድ ቁራጭ፥ ከማር ወለላም ሰጡት፤ ተቀብሎም በላ።» (ሉቃስ 24፥41–43)

## ረብ የለሽ ድራማ?

ኢየሱስ «እጅ እግሬን ተመልከቱ፥ ዳሱትም» እያለ ደቀመዛሙርቱን ካግባባቸው በኋላ ምግብ እንዲሰጡት ጠይቆ የተጠበሰ ዓሣ እፊታቸው ማኘኩና የማር ወለላ መብላቱ ምን ለማረጋገጥ ስለፈለገ ይሆን?

ይህ ሁሉ ለቀልድ ያደረገው፥ የረብ የለሽ ድራማ ድንቅ ተዋናኝ ለመሰኘት የወጠነው ይሆን? በ1819 እኤ ከመወለዴ ከ100 ዓመታት በፊት ስችላሌየር ማቸር (Schlelier macher) ለዚህ ጥያቄ የሰጠው መልስ፥ «በፍጹም፥ ሊሆን አይችልም» የሚል ነበር። ይህ ሰው በዚህ ጉዳይ ላይ የሰጠውን አስተያየት አልበርት ስችዌዘር እንደሚከተለው መዝግቦታል:-

«ክርስቶስ የበላበት ምክንያት መብላት እንደሚችል ለማሳየት ብቻ፥ መመገብ ሳያስፈልገው ሆን ብሎ ያደረገው ከሆነ፥ ድርጊቱ አጭበርባሪነት ይሆናል። ይህ ደግሞ የለየለት አስመሳይነት ነው።»





( In Quest of the Historical Jesus, page 64)

ይህን ጉዳይ አንስቼ ከመጽሐፍ ቅዱስ ማኅበር ሱፐርፋይዘር ጋር ስወያይ እኔ ስችለሌየርማቸርን አላውቀውም። ከሌሎችም እርሱን መሰል ምሁራን ጋር ግንኙነት የለኝም። አልበርት ስችዌዘር እንደመዘገበው፥ እነዚህ ሊቃውንት ከመቶ ዓመታት በፊት በኢየሱስ በመስቀል ላይ የመሞት ዜና ላይ ያላቸውን ጥርጣሬ አስፍረዋል።

## ትንሣኤ የለም

«እናንተ ክርስቲያኖች ምንድን ይሆን ችግራችሁ?» ኢየሱስ ምንም በማያሻማ ቋንቋ መንፈስ እንዳልሆነ–ወደ መንፈስነት እንዳልተለወጠ፥ ከሙታን የተነሳ አካል እንዳልሆነ–ይነግራችኋል። ግና የክርስቲያኑ ዓለም በሙሉ ኢየሱስ ከሙታን እንደተነሳ–ወደ መንፈስነት እንደተለወጠ–ያም ናል። የዋሸው ማን ይሆን? ኢየሱስ ወይስ እናንተ? እያንዳንዱ ክርስቲያን መጽሐፍ ቅዱስን በአፍ መፍቻ ቋንቋው እንዲያነብ ሁኔታዎችን አመቻች ታችኋል። ሆኖም ግን እያንዳንዱ ክርስቲያን መጽሐፍ ቅዱስን አንብቦ የመጽሐፉን መልክት በተቃራኒው እንዲረዳ ተደርጓል። ይህ ግን እንዴት ሊሆን እንደቻለ አልገባኝም? ለምሳሌ እርስዎ መጽሐፍ ቅዱስን በእብራይስጥ አንብበው መረዳት ቢሳነዎት የሚደንቅ አይደለም። በግሪክ አንብበው የጽሑፉ ጭብጥ አልተገለጠልኝም ቢሉ ይህንንም እውነታ ሳይገርመኝ እቀበለዋለሁ። ችግሩ ይህ አይደለም። እያንዳንዱ ክርስቲያን በእናቱ ቋንቋ አንብቦ ካነበበው ነገር ተቃራኒ የሆነ ግንዛቤ እንዲኖረው በልዩ ሥልጠና ይመረዛል። እንደተ ነገራችሁ እንድታስቡ፥ሌሎች አዕምሯችሁ ውስጥ በነደፉላችሁ ፕሮግራም መሠረት ብቻ እንድትረዱ በስልት ተሞልታችኋል። እንዴት ግን ይህ ሊሆን ቻለ?

«እባክዎን ይንገሩኝ? ኢየሱስ ነው የዋሸው ወይስ በአንድ ሺህ ሚሊዮን የሚቆጠሩ ክርስቲያኖች ናቸው የዋሹት? ኢየሱስ ስለ ትንሣኤው የሚሰጠው መልስ ‹በፍጹም አልተነሳሁም› ሲሆን፥ በአንፃሩ ሁላችሁም የምትሰጡት መልስ ‹በፍጹም ተነስተሃል› የሚል ይሆናል። እኛ ሙስሊሞች ማንኛቸውን እንቀበል? የኢየሱስን ቃል ወይስ የደቀመዛሙርቱን ጥርጣሬ? ሙስሊሞች የኢየሱስን ቃል መቀበልን እንመርጣለን። ኢየሱስ እንዳስተማረው:-

«ደቀመዛሙሩ ከመምህሩ፥ … አይበልጥም።» (ማቴዎስ 10፥24)

ይህ ጉዳይ ሬቨረንዱ ከለመዱትና ከሚያስተምሩት፥ ለውይይትም ከሚጋ ፈጡት በላይ ሆነባቸው። በትህትና ይቅርታ ጠይቀው ውይይቱን እንድናቆም አደረጉ። ቢሯቸውን የሚዘጉበት ሰዓት በመድረሱ በሌላ ጊዜ እንድንገናኝ ሁኔታዎችን እንደሚያመቻቹ ቃል ገቡልኝ። ነገር ግን ለትህትና ብለው የተናገ ሩት እንጅ ዳግም ላለመገናኘት እንደወሰኑ ገብቶኛል።

ከቅዱስ መጽሐፍ ማኅበሩ ፕሬዚዳንት ጋር ባካሄድኩት ውይይት ስኬታማ ነበርኩ።ግን የዋጋ ቅናሽ አጣሁ። ከዚህ ቀን በኋላ ከድርጅቱ ይደረግልኝ የነበ ረው ቅናሽ ታገደ። የእኔ የዋጋ ቅናሽ ማጣት ለአንተ ለአንባቢው ጥቅም ካለው ይቅር! አንባቢዬ ከአዕምሮህ ውስጥ ስለ ስቅለት ያለህ የተምታታ አመለካከት ከተስተካከለ አያሌ ሽልማቶችን አግኝቻለሁ።

በመጨረሻ የሚከተሉትን አናቅጽ ከሉቃስ ወንጌል በመጥቀስ ጽሑፌን እቋጫለሁ።

«ይህን ሲነጋገሩ ኢየሱስ ራሱ በመካከላቸው ቆሞ:- ሰላም ለእናንተ ይሁን አላቸው። ነገር ግን ደነገጡና ፈሩ፥ መንፈስም ያዩ መሰላቸው። እርሱም:- ስለምን ትደነግጣላችሁ? ስለምን አሳብ በልባችሁ ይነሳል? እኔ ራሴ እንደሆንሁ እጆቼንና እግሮቼን እዩ፤ በእኔ እንደምታዩት፥ መንፈስ ሥጋና አጥንት የለውምና እኔን ዳስሳችሁ እዩ አላቸው። ይህንም ብሎ እጆቹንና እግሮቹን አሳያቸው። እነሱም ከደስታ የተነሳ ገና ስላላመኑ ሲደነቁ ሳሉ:- በዚህ አንዳች የሚበላ አላችሁን? አላቸው። እነሱም ከተጠበሰ ዓሣ አንድ ቁራጭ፥ ከማር ወለላም ሰጡት፤ ተቀብሎም በፊታቸው በላ።» (ሉቃስ 24፥36-43)